# ኢስላም

## ብቸኛው መለኮታዊ ሐይማኖት



ፀሓፊ፡- ዑስማን ኑሪ ቶፕባሽ
Osman Nuri Topbash

ትርጉም፡ - ሐሰን ታጁ
Translated by Hassen Taju

አሳታሚ
አልበያን ሊሚትድ

# ኢስላም

## ብቸኛው መለኮታዊ ሐይማኖት

Islam, the final Divine Religion

በዶ/ር ሙራድ ኪያት

ትርጉም: አብይ ጣሰው

አርታኢ: ሐሰን ታጁ

አሳታሚ፡ አልበያን ሊሚትድ

ስልክ ቁጥር፡ 0913 87 87 88 ወይም 0911 05 10 25

# ማውጫ

**ርዕስ** **ገጽ**

# መቅድም

**በአላህ ስም እጅግ በጣም ሩህሩህ በጣም አዛኝ በሆነው፡፡**

ስለ ኢስላም ብዙ ነገር ተፅፏል፡፡ በርካታ ብእሮች ከወረቀቶች ተገናኝተዋል፡፡ ሺዎች ጭንቅላቶች ከአላህ የተሰጣቸውን የማሰብ እና የማስተንተን ክህሎት ተጠቅመው የዚህን መለኮታዊ ሐይማኖት ሚስጥራት ለመረዳት እና ለመተንተን ብዙ ደክመዋል፡፡ ይህም ሆኖ ግን የኢስላም የጥበብ ማዕድ ገና አልተነካም፡፡ ወደፊትም ብዙ ይፃፋል፤ ብዙ ይተነተናል፡፡ አዕምሮዎች ገና ብዙ ይደክማሉ፤ ጠቢባንም ብዙ ይደመማሉ፡፡ በኢስላም የማያልቅ ችሮታ የሰው ዘር መመሰጡን ይቀጥላል፡፡

ቱርካዊው ፀሐፊ ሙራድ ካያት ለእርሱ የመሰጡትን የኢስላም ገፅታዎች ባጭር ባጭሩ ከዚህ መፅሐፍ ውስጥ አስፍሯል፡፡ ወንድም አብይ ጣሰውም አሳምሮ ተርጉሞታል፡፡ ሙራድ ጥሩ ፀሐፊ ነው፡፡ አብይም ጥሩ ተርጓሚ ነው፡፡ ለሁለቱም አላህ መልካም ምንዳ ይክፈላቸው፡፡ እኛንም ባነበብነው ተጠቃሚዎች ያድርገን፡፡

መፅሐፉ የኢስላምን ሁለንተናዊ ገፅታ ለመረዳት መልካም አስተዋፅኦ ያበረክታል ብዬ አምናለሁ፡፡ ለሙስሊሞች ብቻ ሳይሆን ሙስሊም ላልሆኑ ወገኖችም ጠቀሜታው ጉልህ እንደሚሆን ይሰማኛል፡፡

ሐሰን ታጁ

መጋቢት 2004

# መግቢያ

## ሰው፣ ዩንቨርስና ፈጣሪ

እስቲ ለአፍታ ቆም ብለን እናስብ። ከየት እንደመጣንና ወደየት እንደምንሄድ እናብሰልስል። ከምንም ነገር አስቀድመን ስለአፈጣጠራችን፣ ስለ አካላዊና መንፈሳዊ ማንነታችን፣ ከፍጥረታት በላይ አኳኋናችን እና እየኖርንበት ያለውን ዩንቨርስ እንመርምር። ይህን ስናደርግ ህይወታችን ትርጉም ይኖረዋል።

እንደምሳሌ ስለምድር በማሰብ እንጀምር። ምንም እንኳ ተመሳሳይ ውሃ በስሮቻቸው ቢስቡም፣ በምድር ላይ ያሉት ተክሎች በቅርፅ፣ በመጠንም ሆነ በቀለም ለቁጥር በሚያታክት አኳኋን የተለያዩ ናቸው። የሁሉም ቅርፃዊ ሆነ ስርአታዊ አቀማመጥ ፍፁም ነው። በምድር ውስጥ በተቀበሩት ሥሮቻቸው ተመሳሳይ ነገር እየተመገቡ እና እየመጠጡ እንዲህ መለያየታቸው የሚገርም አይደለምን?[1]

አይናችንን ወደ ሰማይ ሰክተን ይህን ግዙፍ ምትሀታዊ ዩንቨርስ እንመልከት። ለምሳሌ ፀሐይን እንያት። በምድራችን በ150 ሚሊዬን ኪሎ ሜትሮች ትርቃለች። ምንም እንኳን መካከለኛ መጠን ያላት ኮከብ ብትሆንም እንደ ምድራችን መጠን ያላቸው 1,300,000 ፕላኔቶችን ያክል ትሰፋለች። የውጭ አካሏ ሙቀት መጠን 6,000 ዲግሪ ሴንቲ ግሬድ ሲሆን በውስጧ ያመቀችው ሙቀት እስከ 20,000,000 ዲግሪ ሴንቲ ግሬድ ይደርሳል። በዛቢያዋ የምታደርገው ጉዞ 720,000 ኪሎ ሜትሮች በሰዓት ይሆናል። ይህ ማለት ፀሐይ በአንድ ቀን ውስጥ ብቻ 17,000,280 ኪሎ ሜትሮችን ትጓዛለች።[2]

---

[1] ቅዱስ ቁርአን 13፡4

[2] Prof. Dr. Osman Cakmak, *Bir ˡekirdekti Kâinat (The Universe was a Seed),* pp. 21, 66. (ዩኒቨርሱ ፍሬ ነበር)፣ ገጽ 21,66

በፀሐይ ውስጥ በእያንዳንዱ ሰከንድ 564 ሚሊዮን ቶን ሃይድሮጅን ወደ 56 ሚሊዮን ቶን ሂልየም ይለወጣል፡፡ የ4 ሚሊዮን ቶኑ ልዩነት በተለያዩ ኃይል አይነቶች ከአካሏ ወደ ውጭ የሚተፋ ነው፡፡ በሌላ መልኩ ሲቀመጥ ፀሐይ በእያንዳንዱ ሰኮንድ 4 ሚሊዮን ቶን፣ ይህ በደቂቃ 240 ሚሊዮን ቶን ንጥረ ነገሮችን ታጣለች፡፡ እንግዲህ ፀሐይ በዚህ መልኩ ለሶስት ቢሊዮን አመታት ኃይል ካወጣች (ካጣች) እስከ አሁን ያጣችው ንጥረ ነገር 400,000 ሚሊዮን ቶን ሲባዛ በአንድ ሚሊዮን ይሆናል፡፡ ይህ ግን ካላት ክብደት 1/5,000 ብቻ ነው፡፡
ምድራችን ከዚህች ድንቅ ኮከብ በሙቀቷም እንዳንቀልጥ፣ ጥቅሟንም እንዳናጣ በተመጠነ እና በጥንቃቄ በተሰላ ርቀት ላይ ትገኛለች፡፤ ፀሐይ ኃይሏንና ውበቷን ሳታጣ በምድር ላይ ላሉ ፍጥረታት ለሚሊዬን አመታት ጨረሯን ስትልክ ኖራለች፡፡[3]

እስከሁን ጥቂት ያልንላት ፀሐይ በሚሊኪዌይ ጋላክሲያችን ውስጥ ካሉት 200,000 ከዋክብት መካከል አንዷ ነች፡፡ ይህ ሚሊኪዌይ ጋላክሲ ደግሞ ዩንቨርሱ ውስጥ ካሉት በመቶ ቢሊዮኖች ከሚቆጠሩ ጋላክሲዎች መካከል አንዱ ነው፡፡ ብርሃን በአንድ ሰከንድ 300,000 ኪሎ ሜትሮችን ይሄዳል፡፡ በዚህ ፍጥነት ከአንዱ ጋላክሲ ወደ ሌላው ለመሄድ 100 ሺህ የብርሀን አመታትን ይፈጃል፡፡ አንድ ሰው ከምድራችን ተነስቶ ወደ ሚሊኬዊ ጋላክሲ እምብርት ለመጓዝ ካሰበ በብርሃን ፍጥነት እየበረረ ትሪሊዮን ኪሎ ሜትሮችን ማቆራረጥ አለበት፡፡[4]

እስካሁን ስለተነጋገርንበት እውነታና ስለአካባቢው በደንብ ያጤነ ማንኛውም ግለሰብ ከፍጥረታት ጀርባ አንድ ታላቅና ሁሉን ቻይ የሆነ

---

3 Prof. Dr. Osman Cakmak, *Kâinat Kitap Atomlar Harf (The Universe is a Book, Atoms are Letters),* (ዩንቨርሱ መጽሐፍ ሲሆን፣ አተሞች ፊደላት ናቸው)፣ ገጽ፡ 50

3 Prof. Dr. Osman Cakmak, Bir Cekirdekti kainat (ዩኒቨርሱ ፍሬ ነበር)፣ገጽ 10-12.

4 Prof. Dr. Osman Cakmak, Bir Cekirdekti kainat (ዩኒቨርሱ ፍሬ ነበር)፣ገጽ 10-12.

ፈጣሪ እንዳለ ይረዳል። ይህ ፈጣሪ ይህንን ሁሉ ድንቅ፣ ተዓምራዊ ፍጡራንን የፈጠረበት ዓላማም እንዳለው አብሮ መገንዘቡ አይቀርም። እርሱም (ሰውዬው) እንሰሳዊ ስሜትና ማንነት ብቻ የያዘ ከንቱ ነገር እንዳልሆነ ያውቃል። ጥናቶች እንደሚያሳዩት ከጥንታዊዎቹ ጀምሮ በአሁን ዘመን እስካሉት የተራቀቁትና ዘመናዊ ማህበረሰብ ድረስ ሁሉም ሁሉን ቻይ በሆነ አካል ያምናሉ።[5]

የአላህን መኖር የሚያረጋግጡ ብዙ ምልክቶች አሉ። ሁሉም ሰው ሊያያቸው ከሚችሉ ምልክቶች መካከል የተወሰኑት፡-

1. አንድ ህፃን ከአፀናነሱ ጀምሮ እስከ ዕለተ ሞቱ ድረስ የሚያሳልፋቸው የተለያዩ ለውጦች።
2. የሰዎችን ልብ የሚተረክከው መብረቅና ለሰዎች መልካም ብስራትን ያዘለው እና እርሱን ያካበበው ዝናብ፣ በዐፈር ውስጥ የበሰበሱ ፍሬዎችና ዘሮች ዳግም ህይወት መዝራት
3. የዝናብን መምጣት ዜና የሚያበስሩ ደመናዎችን የሚያሰባስበው ነፋስ፣ የባህርና ሐይቆች መፈጠር፣ የግዙፎቹ ተራሮች በአረግራጊው የምድር ወለል ላይ መቆለል፣ የትናንሽ ከተሞችን ሥፋት የያዙ መርከቦች በውቅያኖሶች ላይ መንሻለል። [6]
4. በምድርም ሆነ በሰማያት ያሉ ነዋሪዎች መኖር።

ታላቁ ጀላሉዲን ሩሚ እንዲህ ይላል “ልጄ ሆይ! በግርግዳው ላይ የተፃፉት ፊደላት  ፀሐፊ ፃፋቸው ብሎ ማሰቡ ይቀላል ወይስ በራሳቸው ተሰደሩ?" (መትናዊ ቅፅ 6፡ ገፅ 368)

[5] Prof. Dr. Osman Gunay Tumer, ዲን (Din) Diyanet Islam Ansiklopeds (የኢስላም ባህር እውቀት) (የቱርክ ሪፐብሊክ፣ የሐይማኖት ጉዳይ ኃላፊ፣) ኢስታንቡል 1994 IX ገጽ 315-317.

[6] አርሩም 30፡20-46፣ አሽሹራ 42፡29 እና  32፣ ያሲን 36፡ 33-41፣ አልበቀራ 2፡ 22 በተጨማሪም ኢብራሂም፣ 14፡ 32-33፣ አርሩም 30፡ 40 እና 48 እና 54፣ ፋጢር 35፡ 9፣ አል ሙዕሚን 40፡65 እና 64 እና 79፣ አል ጃሲያ 45፡ 12፣ አጥጦለቅ 65፡12 ይመልከቱ።

"አንተ ሞኝ ሰው ሆይ! ህንፃዎች በአናፂዎች ታነፁ ብሎ ማሰቡ ትርጉም ይሰጣል ወይስ እንደው ድንገት ተገኙ? ድንቅ የጥበብ ስራ ውጤት በአይነ ስውር ተሰራ የሚባለው ለሃሳብ ይቀላል ወይስ በዓይናማ ጥበበኛ?" (*መትናዊ ቅፅ* 6፣ *አንቀፅ* 369 -371)

"ጥልፎች፣ *ሥዕሎች አመንንም ካድንም የጥበበኞች ውጤቶች ናቸው፡፡ አንድ ማሰሮ ለመስራት ሸክላ ሰሪው በገል አፈር ተጨማልቆ ነው፤ አፈሩ ራሱ ቦክቶ ተጠፍጥፎ፣ በራሱ ቅርፅ አይዝም፡፡ የእንጨት ስራ የአናፂው ጥበብ ውጤት ነው፡፡ የትኛውም ዛፍ በራሱ ተልጎ፣ ተቆርጦ፣ ተቆራርጦ ጠረጴዛ አይሆንም፡፡ ያለ ልብስ ሠፊው የጨርቅ አልባሳትን እናስባለን? አንተ ብልሁ ሰው! ያለእንስራ ተሸካሚዋ እንዴት ውሃውን እቤታችን እናገኘዋለን?.... እናም ብልሁ ሰው! አንተም የታላቁ እና ብቸኛው ፈጣሪ ሥራ ውጤት ነህ!፡፡ አንድ ቀን ዓይኖችህን የጋረደው የድንቁርና ሞራ ሲገፈፍ፣ የድብቅ ዓለማት ዕይታ ቋጠሮ ሲፈታ፣ የጥበብ ስራ በጠቢቡ እጅ እንዴት ከአንዱ ሁኔታ ወደ ሌላ እንደሚለወጥ ታያለህ!"* (*መትናዊ ቅፅ* 6፣ *አንቀፅ* 3332-3341)[7]

የቁሶች *መገኘትና በመካከላቸው ያለው ፍፁማዊ ግንኙነትና የእንቅስቃሴ ስርዓት "የድንገተኝነት ውጤት ነው" ተብለው የሚብራሩ አይደለም፡፡*

*የፕሪስተን ዩኒቨርሲቲው የሥነ ሕይወት* (ባይሎጂ) *እና ስፍነተ እንስሳተ ተመራማሪ* (ዚኦሎጂ) *ኤድዊን ኮንኪል* (1861-1952) *እንዲህ ብሎ ነበር፡- "ሕይወት ያለው አካል በድንገት የመገኘቱ እድል፣ የካምብሪጅ*

*መዝገበ ቃላት በማተሚያ ቤት ፍንዳታ ከመፈጠሩ ዕድል ጋር እኩል ነው*"[8]

---

[7] ፋጢር 35፡3

[8] *The Evidence of God,* p. 174; Prof. Dr. Vahidüddin Han, *Islâm Meydan Okuyor (ኢስላም ሲያነቃቃ)* **ገጽ** 129.

## ሰውና ኃይማኖት

ኃይማኖት የሰው ልጅ በዚህች ምድር ላይ ሲኖር እንዴት መኖር እና ወደ መጪው ዓለም ሲጓዝ በምን አይነት ሁኔታ መሆን እንዳለበት መረጃ የያዘ ነው። ኃይማኖት ሰው ማንንም ሳይጎዳ ሊያኖረው የሚችል ህግጋት የያዘ ነው። በዚህች ምድር ላይ የሚኖርባትን አጭር ጊዜ በሰላም እንዲያሳልፋት የሚያስችለውን፣ በመጪውም አለም ስኬታማ የሚያደርገውን መብትና ግዴታዎች የሚያሳውቀውና የሚያስገነዝበው ነው ኃይማኖት።

አላህ (ሱ.ወ) ዩንቨርሱን በተለያዩ ፍጡራን ሞልቶታል። የሰው ልጅ ከነዚህ ፍጥረታት የተለየ ቦታ አለው። ሰው ሌሎች ፍጥረታት የሌሉዋቸው የእርሱ ብቻ የሆኑ ሥጦታዎች አሉት - ዕውቀት፣ ፈቃድ፣ ብልሃት (ጥበብ)፣ ውስብስብ ኃሳቦችን መፀነስና መረዳት፣ የነገሮች ባለቤት መሆን እና መራቀቅ የሰው መገለጫ ባህሪያት ናቸው። ሆኖም እነዚህ ሥጦታዎች ባለመንታ ሥለት ናቸው። መልካም ሥለታቸውን ከተጠቀምን የተዘበራረቀውን እናስተካክላለን፣ ለሰው ልጆች በጎ አጋጣሚዎችን እናመቻቻለን፣ ኑሮን ምቹ እናደርጋለን። ነገር ግን በተቃራኒው ሥለት ከተጠቀምን ቀውስና ስርዓት አልበኝነት እናነግሳለን። ዓለማችን ያስተናገደቻቸውና እያየቻቸው ያሉ አሰቃቂ ጭካኔዎችና ታላላቅ ጦርነቶች በዚህ ስለት ከሠይጣን ኮሮጆ ተቀርድደው እንዲያፈተልኩ የተደረጉ ናቸው።

ስለሆነም እነዚህን ሥጦታዎች በጎ ውጤት በሚያመጡበት መልኩ እንዲቅጣጩ ሌላ ኃይል ያስፈልገናል። ይህ ኃይል እውነተኛ ኃይማኖት ይባላል። አንድ ነገር ግን መዘንጋት የለብንም። አላህ (ሱ.ወ) ፃድቅና መልካም እንድንሆን የሚፈልገው ለህልውናው ስለሚያሥፈልገው አይደለም። ሰናይም ብንሆን እኩይ ምንጠቀመው ሆነ ምንጎዳው እኛው ነን። ለእርሱ የሚተርፈው ነገር የለም። "እኛ ሰዎች ኃይማኖታዊ

ትዕዛዛትን መከተል ያለብን በመጪው ዓለም ስለሚጠቅመን ብቻ ሳይሆን፣ በዚህም ዓለም ደስተኞች ሆነን ለመኖር ጭምር ነው።" [9]

የሰው ልጅ የተፈጠረው አምላኩን እንዲያውቅና እርሱን ብቻ ለማምለክ እንደሆነ መለኮታዊ ኃይማኖቶች በሙሉ ያስተምራሉ።[10]

ኃይማኖትን ለሰዎች ያስተዋወቁ ሰዎች ነቢያት ይባላሉ። ኢስላም ለነዚህ ነቢይ ዕውቅና ከመስጠትም አልፎ በነርሱ ማመንን የሙስሊምነት ቅድመ ሁኔታ አድርጎ አስቀምጧል። እንደ ኢስላም አስተምህሮት በነቢያት መካከል ያልተቋረጠ ሰንሰለት አለ። እያንዳንዱ ነቢይ የቀደመውን ነቢይ አስተምሮት አፅንቶ ስለተቀጣዩ ነብይ ብስራት ነግሮ እንዳለፉ ያስተምራል።[11]

ስለሆነም የነብዩ ሙሐመድን (ሰ.ዐ.ወ) ነብይነት የተቀበለ ከርሳቸው በፊት ያለፉትን ነቢያት ተቀብሏል ማለት ነው።

ሐጢብ ቢን አቢ ቤልታዓህ (ረ.ዐ)፣ የአላህን መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) የእስልምናን ተቀበል የግብዣ ደብዳቤ ለግብፁ ገዢ ሙቀውቀስ ሲሰጠው እንዲህ ነበር ያለው፡-

"አላህ ለሰዎች ወደመረጠው ኃይማኖት ኢስላም እንጋብዝኃለን። ሙሐመድ ሙስጠፋ (ሰ.ዐ.ወ) አንተን ብቻ ሳይሆን የሰውን ዘር ወደ ኢስላም እየተጣሩ ነው። ከሰዎች መካከል ክርስቲያኖች በተሻለ ቀርበዋቸዋል። ሙሳ የዒሳን መምጣት እንዳበሰረ ሁሉ ዒሳም የሙሐመድን መምጣት ተናግሯል። እኛ አንተን ወደ ቁርአን የመጥራታችን ምሳሌ፤ አንተ የተውራትን ሰዎች ወደ እናንተ መፅሐፍ (ገዢው ክርስቲያን ነበር) እንደምትጠራ ነው።

---

9 Prof. Dr. M. S. R. el-Buti, **የኢስላም አቂዳ** *(Islâm Akâidi)*, ገጽ. 71-76.

10 *ኦሪት ዘ ፍጥረት* 20/2-3; *ኦሪት ዘ ዳግም*, 6/4-5; *ማቲዎስ ወንጌል* 4/10; *የሐዋሪያት ስራ*, 17/26-28; **ቅዱስ ቁርዓን አዝ-ዛሪያት** 51: 56.

11 Prof. Dr. O. F. Harman, Article: "Islam", *Diyanet Islâm Ansiklopedisi – (የኢስላም ባህረ ዕውቀት፣ በቱርክ ሪፐብሊክ የኃይማኖት ጉዳዮች ኃላፊ) ኢስታንቡል2001፣ XXIII) 4*

እያንዳንዱ ሰው በዘመኑ የመጣውን ነብይ የመከተል ግዴታ አለበት። በነብዩ ሙሐመድ ዘመን ከደረሱ ሰዎች መካከል አንተ አንዱ ነህ።

አንተን ወደ ኢስላም መጥራታችን ከኢየሱስ ኃይማኖት አያወጣህም። እንደውም የእርሱን ትንቢት እንድትቀበል እየጋበዝንህ ነው"[12]

በቶሮንቶ ዮርክ ዩንቨርሲቲ ፕሮፌሰር የሆነው ቲሞቲ ጊያኖቲ (Timothy Gianotti) በንግግሩ እስልምናን በመቀበሉ የቀድሞው ኃይማኖቱን እንዳልተወ፤ የቀድሞ ኃይማኖቱን የሚመለከተው ወደ እስልምና እንደሚያሻግር ድልድይ እንደሆነ አብራርቷል። በተጨማሪም ስለ እስልምና ሲያስረዳ የክርስትናን ግብ ጨምሮ የያዘ ሁሉን አቀፍ ኃይማኖት እንደሆነ ተናግሯል። "የኢስላም ዓላማ የተወሰኑ ሰዎች ስብስብ ብቻ ሳይሆን የሰውን ዘር በሙሉ ከአላህ ዘንድ ዋጋ ወዳለው ስብስብ መለወጥ ነው" [13] ነብያችን(ሰ.ዐ.ወ) ሲናገሩ "ነብያት ወንድማማቾች ናቸው" ብለዋል።[14]

ይህ ወንድማማችነት ሁሉም ትክክለኛ ሐይማኖቶችና ተመሳሳይ መርህ እንዳላቸው የሚያመለክት ነው። እነዚህ ከመጀመሪያ ነብይ አደም ጀምሮ እስከ መጨረሻው ድረስ ያሉት ነቢያት የሰበኩት ኃይማኖት በእምነትና መሠረታዊ ሞራል እሴቶች ተመሳሳይ ሲሆን የአምልኮ አፈፃፀም ተግባራት ግን እንደ ወቅቱ ተጨባጭ የሚለወጡ ናቸው።[15]

ከአምላክ ሊሰጥ ሚችለው አንድ ትክክለኛ ሐይማኖት ብቻ ስለሆነ በመለኮታዊ ሐይማኖቶቹ ዘንድ ተመሳሳይ ነገር ሊኖር እንደሚችል

---

12 በሐቲብ እና ሙሳብኪስ መካከል የተካሄደውን ረዘም ያለ ውይይት ለማንበብ ኢብን ከሲር አል-ቢዳይ IV, 266-267; Ibn-i Sa'd, I, 260-261; Ibn-i Hacer, *el-Isâbe*, III, 530-531.

13 Ahmet Boken - Ayhan Eryiğit, Yeni *Hayatlar (አዲስ ሕይወት)*, I, pg.15.

14 ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) እንዳሉት "ለማርያም ልጅ ከሰዎች ሁሉ የቀረብኩ ነኝ። ነቢያት በእናት የሚለያዩ ከአንድ አባት የተገኙ ወንድማማቾች ናቸው። በእርሱና በእኔ መካከል ነቢይ አልነበረም።" " (Bukhari, Anbiya, 48; Muslim,Fedail, 145)

15 Prof. Dr. O. F. Harman, Article: "Islam", *Diyanet Islâm Ansiklopedisi – (የኢስላም ባህረ ዕውቀት፣ በቱርክ ሪፐቡሉክ የኻይማኖት ጉዳዮች ኃላፊ) ኢስታንቡል2001፣ XXIII)* 3.

እሙን ነው። ለምሳሌ በኢስላም ለአላህ መስገድ ግዴታ እንደሆነው ሁሉ በመፅሐፍ ቅዱስ ውስጥም ተመሳሳይ ህግ እናያለን።

"ኑ እንስገድ ለእርሱ እንገዛ፤ በእርሱ ባደረገን በእግዚአብሔር ፊት እንበርከክ፣ እርሱ አምላካችን ነውና።" (መዝሙረ ዳዊት 95፡6)

"... እነርሱም በግንባራቸው ወድቀው አምላክ ሆይ አንተ የሰው ሁሉ ነፍስ አምላክ ..." (ዘሁልቅ 16፡- 20-22)

"ሙሴም ፈጥኖ ወደ መሬት ተጎነበሰና ሰገደ......... "(ዘፀአት 34፡8)

"ጥቂት ወደፊት እልፍ ብሎ በፊቱ ወደቀና ሲፀልይ ......... (ማቴዎስ ወንጌል 26፡39)

# ምዕራፍ አንድ

# የኢስላም መለያ ባህሪያት

## የአንድ አላህ (ተውሒድ) አምልኮ

ሁሉም መለኮታዊ ኃይማኖቶች የአምላክን አንድነት ያስተምራሉ። እርሱን የሚመስል አንዳች ነገር የለም።" ነብዩ ኢብራሒም የአላህን አንድነት ለአባቱ አዛር አስረግጠው ነበር ያስረዱት።[16] የአይሁድ ኃይማኖት መሠረታዊ መርህ የአምላክ አንድነት ነው ። እንደ ተውራት (ቶራህ) አስተምሮ የመጀመሪያው ሰው አዳምና ልጆቹ፣ ኖኅ[17]፣ አብርሐም፣ ይስሐቅ ፣ያእቆብ እና ዮሴፍ ሕይወታቸውን በሙሉ ወደ አንድ አምላክ ሲጣሩ ያሳለፉ ነበሩ። ለነብዩ ሙሴ በተሰጠው በአስርቱ ትዕዛዛትም ሆነ በሌሎች የተውራት ህግጋት እጅግ አፅዕኖት የተሰጠው ጉዳይ የአምላክ አንድነት ነው።[18] ለነብዩ ዳዊት የተገለጠውም መዝሙር ለአንድ አምላክ የተደረገ ፀሎት ነበር። ነብዩ ኢየሱስም የመጀመሪያው (ቀዳሚው) ኃይማኖታዊ ትዕዛዝ አንድ አምላክን ብቻ ማምለክ ነው ሲል አፅእኖት ሰጥቶ አስተምሯል።[19]

እጅግ የተጋነነ ምድራዊ አረዳድ ያዳበሩት አይሁዶች የአይሁዳዊነትን የአምላክ ፅንስ ኃሳብ ሰዋዊ እንዳደረጉት ሁሉ፤ የክርስቲያኖችም ለኢየሱስ ያላቸው የተጋነነ ፍቅር ሰብአዊ ፍጡሩን አምላክ አድርጎ፣ ስላሴ የሚባል እንግዳ ነገር እንዲፈጠር አድርጓል። ኢስላም እንደቀድሞው ሁሉ አሁንም የአላህን ብቸኝነት፣ አንድነትና "ልዩነት" አፅዕኖት በመስጠት እና በትክክለኛው የአምላክ ፅንሰ ሀሳብ ላይ

---

[16] ቅዱስ ቁርዓን መርየም 19፡ 42-47 19፡ 42-47.

[17] ኦሪት ዘፍጥረት 1:26-28; 4:26; 6:9.

[18] ኦሪት ዘፍጥረት 20:2-3; Deuteronomy, 6:4-5.

[19] የማርቆስ ወንጌል 12:28-29.

የተለጣጠፉ ሰዋዊ ድሪቶዎችን በማፅዳት አይሁዶችንና ክርስቲያኖችን ወደ አንድ አምላክ አምልኮ (ተውሒድ) ይጠራል፡፡[20]

ምክንያት እና የተፈጥሮ ማስረጃ የሚያረጋግጡ ይህንኑ የኢስላም ጥሪ ነው፡፡

﴿ مَا ٱتَّخَذَ ٱللَّهُ مِن وَلَدٍ وَمَا كَانَ مَعَهُۥ مِنْ إِلَٰهٍ ۚ إِذًا لَّذَهَبَ كُلُّ إِلَٰهٍۭ بِمَا خَلَقَ وَلَعَلَا بَعْضُهُمْ عَلَىٰ بَعْضٍ ۚ سُبْحَٰنَ ٱللَّهِ عَمَّا يَصِفُونَ ﴿٩١﴾ ﴾ المؤمنون: ٩١

«አላህ ምንም ልጅን አልያዘም (አልወለደም)፡፡ ከእርሱም ጋር አንድም አምላክ የለም፡፡ ያን ጊዜ (ሌላ አምላክ በነበረ) አምላክ ሁሉ በፈጠረው ነገር በተለየ ነበር፡፡ ከፊላቸውም በከፊሉ ላይ በላቀ ነበር፡፡ አላህ ከሚመጥኑት ሁሉ ጠራ፡፡»

**(አል-ሙዕሚን :91)**

﴿ لَوْ كَانَ فِيهِمَآ ءَالِهَةٌ إِلَّا ٱللَّهُ لَفَسَدَتَا ۚ فَسُبْحَٰنَ ٱللَّهِ رَبِّ ٱلْعَرْشِ عَمَّا يَصِفُونَ ﴿٢٢﴾ ﴾
**الأنبياء: ٢٢**

«በሁለቱ (በሰማያትና በምድር) ውስጥ ከአላህ ሌላ አማልክት በነበሩ ኖሮ. በተበላሹ ነበር፤ የዐርሹ ጌታታ አላህም ከሚሉት ሁሉ ጠራ፡፡»

**(አል-አንቢያ 21:22)**

የባለ ብዙ አምላክ አስተሳሰብ ፅንስ ሐሳብ የደካማነት፣ ኢፍፁማዊነት እና ፍጡራዊ ባህሪ አመላካቾች ስለሆኑ አምላክ አንድ እና ብቸኛ መሆኑ ግድ ነው፡፡

የአምላክን ብቸኝነትና አንድነት ከዚህም አንፃር መረዳት እንችላለን፡- የዝናብ መዝነብ፣ በምድር ላይ ተስበው የሚበቅሉ ቲማቲም ወይም ዱባ፣ በዛፎች ላይ የሚበቅሉ አፕል (ፖም) ሆነ ብርቱካን በየትኛውም ቦታ ይብቀሉ በዝርያቸው ቅርፅና ቀለም ተመሳሳይ ናቸው፡፡ ይህ ከአንድ

[20] Ali Imran (The Family of Imran), 3: 64. Prof. Dr. O. F. Harman, Article: "Islam", *Diyanet Islâm Ansiklopedisi - Encyclopedia of Islam (Republic of Turkey, Presidency of Religous Affairs),* Istanbul 2001, XXIII, 4.

አካል የሚወጣ አስተሳሰብ ምንጭ ነው። የአላህን አንድነት የሚጠቁም ተፈጥሮዋዊ እውነታ ነው።

በኢስላም እጅግ ከባባድ ተብለው ከሚፈረጁ ኃጢያቶች መካከል ዋነኛዎቹ ከዚሁ ከአንድነቱ ጋር የተያያዙ ናቸው። የእነርሱን መኖር አለመቀበል፣ በእርሱ ላይ ማጋራት እና የእርሱን ብቸኛ ምንነት፣ ማንነት ሆነ ባህሪያት ለፍጡራን መስጠት ታላላቅ ኃጢያቶች ናቸው። "ሽርክ" ማጋራት የኃጢያቶች ሁሉ ኃጢያት ነው። አምላክም የገለፀው እንደዚሁ ነው።[21]

ምንም እንኳን አላህ (ሱ.ወ) የትኛውንም ኃጢያት እንዳሻው ቢምርም በእርሱ ላይ እያጋራ የሞተን ሰው ፈፅሞ አይምረውም።[22i] ከሽርክ ሀጢያት ብቸኛው ማምለጫ በህይወት ሳሉ እርግፍ አድርጎ መተውና ተውሂድን መቀበል ነው።

## ኢስላም የተፈጥሮ ኃይማኖት ነው፣ከምክንያታዊነት ጋር የሚጋጭ አይደለም

ኢስላም በዓለም ዙሪያ ያሉ ሰዎችን ይጣራል። መሠረታዊ የሀይማኖቱ ህግጋት ክልላዊ፣ ቁንፅል የሰዎችን ባህሪያት ብቻ የሚያናግሩም ሆነ ጊዜያዊም አይደሉም። የህግጋቱ መሠረት የሠዎች ተፈጥሮ፣ ተፈጥሮዋዊ አዝምሞትና ፍላጎት ላይ ነው። በዚህ ምክንያት ኢስላም በጊዜያዊ ሂደት ያልተገደበ ተፈጥሮዋዊ ኃይማኖት ነው። የእምነቱ መርሆዎች የማይጨበጡ ሚስጥራት ሳይሆኑ በእውቀት፣ ምክንያት እና ገሀዳዊ ዕውነታ ላይ የተመሠረቱ ናቸው። ኢስላም ከሳይንሳዊ እውነታዎች ጋር አይጋጭም። ኢስላማዊ የአምልኮ ሆነ አምልኳዊ ያልሆኑ ትዕዛዛትን ስንመረምር ትዕዛዛቱ ከሠዎች ተፈጥሮ ጋር የተሰናሰሉ ናቸው።

---

21 Luqman, 31: 13; An-Nisa (Women), 4: 48.
22 An-Nisa (Women), 4: 48, 116.

ዕውቀትና ምክነያት የሠዎች ልዩ መገለጫ ባህሪያት ናቸውና ቅዱስ ቁርአን፣ ሰዎች እነዚህን ልዩ ባህሪዮቻቸው እንዲጠቀሙ ይጎተጉታል፡፡ ለዕውቀትና አብሰልስሎ ትኩረት ይሰጣል፡፡ በ750 የቅዱስ ቁርአን አናቀፅት ሰዎች እንዲያስቡ እንዲመራመሩ እና እውቀታቸው በምርጥ አኳኋን እንዲጠቀሙ ይጋብዛል፡፡[23]

ሰዎች ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) አንተንና አላህን እንድንቀበል ከፈለግህ "ተዓምር አሳየን" ብለው ሲጠይቋቸው፣ አላህ (ሱ.ወ) ተዓምራትን ከመጠበቅ ሰማያትንና ምድርን እንዲመለከቱና ስለእነርሱ እንዲያስቡ አበረታቷል፡፡

ኢስላም ለአእምሮ ሚና ከፍተኛ ዋጋ ስለሰጠ ይህንን የአእምሮን ሚና የሚያደናቅፉ ነገሮችንም ከልክሏል፡፡ አልኮልና አደንዛዥ ዕፆች በኢስላም ፈፅሞ የተከለከሉ ናቸው፡፡ ሰው መጠጥ ጠጥቶ እንደ አልባሌ ነገር የትም ከሚንከባለል ከነክብሩ ቢቆይ፤ በአደንዛዥ እፅ ናውዞ በየስርቻው ከሚልከሰከስ ሕያው ቢሆን የትኛውም ሰው የሚቀበለው ነው፡፡ ስካር እና ስንፍና ምንም ጥቅም የላቸውም፡፡

ከሐይማኖቱ ተፈጥሮዋነት የተነሳ የኢስላም ሕግጋት ለአተገባበር ቀላል ናቸው፡፡ ለሰው ልጅ ፈታኝ የሆኑ፣ ለትግበራ አዳጋች ሕግጋት በኢስላም ውስጥ አይገኙም፤ ቦታም የላቸውም፡፡ ለምሳሌ፡-

- ከሶላት በፊት መንፃት (ውዱዕ ማድረግ) ግድ ነው፡፡ ውዱዕ በዋነኝነት ሚፈፀመው በውሃ ቢሆንም ውሃ ከሌለና ውሃ ለመጠቀም የማያስችል የጤና እክል ካለ በንጹህ አፈር (ተየሙም) መጠቀም ይቻላል፡፡
- አንድ ሰው ቆሞ ሶላት መስገድ ካልቻለ ተቀምጦ፣ ባይችል ተኝቶ፤ ተኝቶ እንኳን ካቃተው በጥቅሻ መስገድ ይችላል፡፡
- መፆም ካልቻለ፤ ለጾሙ እንቅፋት የሆነው ችግር ሲወገድ መፆም ወይም ችግሩ ቋሚ ሲሆን በገንዘብ መተካት ይችላል፡፡

23 Ayşe Sucu et al., *Gençlik ve Din (Youth and Religion),* p.220.

- ዘካ የሚከፈለውም ሆነ ሐጅ የሚደረገው አቅም ሲኖር ነው፡፡
- ሰዎችን ሙስሊም የማድረግ ግዴታ የለም፡፡ በአማኞች ላይ ያለው ግዴታ በተቻለ መጠን እምነቱን አብራርቶና ሳቢ አድርጎ ማቅረብ ነው፡፡

## የነፍስ አባት የለም

አንድ የኢስላም ሊቅ፡- "ወደ አላህ መቃረቢያው መንገድ ከፍጥረቱ እስትንፋስ ጋር የተያያዘ ነው" ብሎ ነበር፡፡ ሁሉም ሰው ከአላህ (ሱ.ወ) በቀጥታ የመገናኘት መብት አለው፡፡ እያንዳንዱ ሰው  በፀሎት ወደ አላህ መጣራትና ማርታ መለመን ይችላል፡፡ የትኛውም ሰው በእውነተኛ ፍላጎት አላህን ከፈለገው ከፊቱ ያገኘዋል፡፡

አምላክ ባሪያዎቹ ወደ እርሱ እንዲጣሩና ለኃጢያታቸው ይቅርታ እንዲጠይቁ ያበረታታል፡፡ እጅግ ሩህሩህ ነኝ ብሏልና ይቅር በለኝ ያለውን ባሪያውን ኃጢያት ይምራል፡፡ የሚለመነው፣ የሚጠየቀው፣ ምላሽም የሚሰጠው አላህ ብቻ ነው፡፡ የሚችለውና የሚያደርገው እርሱ ብቻ ነውና፡፡ ማንኛውም ፍጡር ይህንን የአላህን ብቸኛ ስልጣን መውሰድ አይችልም፡፡ ይህንን የአላህ መብትና ስልጣን ለፍጡራን መስጠት ሽርክ ይባላል፡፡

በኢስላም ሰዎችንና አምላክን የሚያገናኝ የነፍስ አባት ፅንሰ ሀሳብ የለም፡፡ ሁሉም ሙስሊም ስለኃይማኖቱ የተቻለውን ያህል የማወቅ መብት አለው፡፡ ሙስሊሞች ለሶላት ሲሰባሰቡ ሶላቱን እንዲመራላቸው (ኢማም እንዲሆንላቸው) ከመካከላቸው አዋቂውንና ፃድቁን ይመርጣሉ፡፡ በኢስላም ፃድቃን (ዓሊሞች) ኃይማኖቱን ከማብራራትና ሰዎችን ወደ ቀጥተኛው መንገድ ከማመልከት የበለጠ ሚና የላቸውም፡፡ ኃጢያትን ይቅር የማለት፤ በፈጣሪና በሰው መካከል ምልጃ መፈፀምም ሆነ በፈጣሪ ምትክ ሆኖ የግለሰቦችን ፀሎት የመመለስ ሥልጣንም ሆነ መብት የላቸውም፡፡

የጣኦት አምልኮ የሚጀመረው ሰዎች በእነርሱና በፈጣሪ መካከል አማላጅ ሲያስቀምጡ ነው፡፡ የመካ ጣኦት አምላኪዎች ለጣኦት አምልኮዋቸው ሲሰጡት የነበረው ምክንያት ይህን ነበር፡፡ ጣዖታትን የምናመልከው ወደ አላህ እንዲያቀርቡን ነው፡፡[24]

በመጨረሻም ለእነዚህ አማላጅ ጣዖቶች መለኮታዊነት አላበሱዋቸው፡፡

## ኢስላም የቁስንና የመንፈስን፤ የዚህችንና የመጪውን ዓለም ሚዛን የጠበቀ ነው

ኢስላም ለሚዛናዊነት ከፍተኛ አፅንኦት ሰጥቷል፡፡ ለአንደኛው የህይወት እውነታ (ገፅታ) ብቻ አፅንኦት ሰጥቶ ሰውንም ሆነ ህይወትን ወደ አንድ ጎን አያማልልም፡፡ የሰውን ልጅ ሁለንታዊ ባህሪ የፈጠረው አላህ ስለሆነ አንዱን ከአንዱ የሚያበላልጥበት ምንም ምክንያት የለውም፡፡ አንዱን የህይወት ምንነት (ገፅታ) አንጠልጥሎ ሌላውን መጣል ትክክል አይደለም፡፡ ለሁሉም የህይወት እና የዓለም ምንነት አስፈላጊውን አትኩሮት መስጠትና ፍትሃዊ በሆነ መንገድ መቅረብ ግድ ይላል፡፡

እይታችንን ከዚህ አንፃር ካስተካከልነው፤ ይህች ዓለም ለመጪው ዓለም ስኬት ወሳኝ እንደሆነች እንገነዘባለን፡፡ ስለሆነም አንድ ሰው የአላህን ደስታ ማግኘት ከፈለገ፤ የዚህች ዓለም ቆይታውን በአግባቡ መጠቀም አለበት፡፡ ሆኖም የትኛውም ሰው መርሳት የሌለበት መጪው ዓለም የህይወቱ ዋና ግብ መሆኑን ነው፡፡

ዓለማዊው አስተሳሰብ ይህችን ምድር ብቻ ሙጥኝ እንዳለ ሁሉ፤ ባህታዊዎቹ ደግሞ ከመጪው ዓለም ውጪ የሚታያቸው የለም፡፡ በመሆኑም ሁለቱም አመለካከቶች የሰውን ሁለንታዊ ፍላጎቶች ምሉዕ አድርገው አልመለሱም፡፡ ለአንዱም ዓለም ሲባል ሌላኛው መሰዋት የለበትም፡፡ ሁለቱም አስፈላጊ ስለሆኑ ለሁለቱም ዓለማት ትክክለኛ እና ወጥ አስተሳሰብ ሊኖር ያስፈልጋል፡፡

---

[24] Az-Zumar (The Companies), 39: 3.

መንፈስና አካል የሰው ልጅ ሁለት ጎኖች ናቸው። ነፍስ ወሳኝ ብትሆንም ማደሪያዋ አካል የዛኑ ያህል አስፈላጊ ነው። ሁለቱ በአንድ ላይ ሲሆኑ ብቻ ነው ህይወት ትርጉም ያላት፤ አንዳችም ነገር ማድረግ የሚቻለው። ስለዚህ መንፈስ መንፈስ እያሉ አካልን መጉዳት ፈፅሞ ስህተት ነው። ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ከፈጣሪያችን ፊት ስንቀርብ ከምንጠየቃቸው ጥያቄዎች መካከል ጤናችንን እንዴት እንደተጠቀምንበት እንደሆነ ተናግረዋል።[25]

ሌላው ይቅርና ኢስላም በአምልኮ ተግባራት ላይ እንኳ ሚዛን እንዳንስት አሳስቧል። ስንሰግድ፣ ስንጾምም ሆነ ስንመፀውት እኛን በሚጎዳ መልኩ መሆን እንደሌለበት አስገንዝቧል።[26]

## ኢስላም ትምህርትን ያበረታታል

እስከዛሬ ድረስ በኢስላምና በሳይንስ መካከል ምንም ዓይነት ግጭት የለም፤ ወደፊትም አይኖርም። ኢስላም በታሪኩ እንኳን ከሳይንስ ጋር ሊጋጭ ይቅርና፤ ሳይንሳዊ ምርምሮችን አበረታቷል። በወንዶችም ሆነ በሴቶች ላይ እውቀትን መፈለግ (መማርን) ግዴታ አድርጓል። ሳይንሳዊ ግኝቶች ከኢስላም እውነታ ጋር ተጋጭተው አያውቁም፤ እንደውም አስተምሮቱን ሲያስረግጡ ኖረዋል። ሳይንስ አላህ (ሱ.ወ) ነገሮችን የፈጠረበትን ሕግ ለመረዳት የሚጥር ስለሆነ ከኢስላም ጋር የሚጋጭበት ምንም ምክንያት የለውም። ኢስላም ከአላህ (ሱ.ወ) ለሰዎች የተሰጠ፤ እስከ መጨረሻውም ዕለት ሳይበረዝ በሰጪው አካል ተጠብቆ የሚቆይ መለኮታዊ ኃይማኖት ነው። ሳይንስ የሚያጠናው ሕግና የኢስላም ምንጭ አንድ ነው። ሳይንስ ብቃቱ ሲሻሻል፤ ከቀን ወደ ቀን እንዳዲስ ግኝቶችን ለሰዎች ሲያስተዋውቅ፤ የአላህ (ሱ.ወ) ታላቅነት፣ ገደብ የለሽ እውቀቱ ይበልጥ ግልፅ እየሆነ፣ ሰዎችም ስለአላህ ያላቸው ዕውቀት እየጠነከረ መምጣቱ አይቀርም። በዚህ ምክንያት ሳይንስ የኢስላም አንደኛው ክፍል ነው።

---

[25] Tirmizî, Kıyamah, 1/2417.

[26] See Bukhari, Savm 55, 56, 57, Tehejjud 7, Anbiya 37, Nikah 1, 89; Muslim, Siyam 181-193; Abu Dawud, Savm, 55/2428.

የአላህን (ሱ.ወ) ሁሉን አዋቂነት የሚገልፁ፤ ድብቁንም ሆነ ግልጹን ነገር እንዴት እንደሚያውቅ የሚያሳዩ ውብ ስሞች አሉት። የአላህም ባሪያ ይህንን መለኮታዊ ባህሪ የሚቋደስበትን አጋጣሚዎች በፍፁም ሊያሳልፍ አይገባም። ዕውቀትን በመፈለግ ላይ እንዲተጉ የሚያሳስቡ ብዙ የቁርአን አንቀፆችና የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ንግግሮች አሉ።

﴿ وَقُل رَّبِّ زِدْنِي عِلْمًا ﴾ طه: ١١٤

«ጌታዬ ሆይ! ዕውቀትንም ጨምርልኝ» በል።›› (ጦሃ:114)

﴿ يَرْفَعِ اللَّهُ الَّذِينَ آمَنُوا مِنكُمْ وَالَّذِينَ أُوتُوا الْعِلْمَ دَرَجَاتٍ وَاللَّهُ بِمَا تَعْمَلُونَ خَبِيرٌ ﴾ المجادلة: ١١

‹‹አላህ ከናንተ እነዚያን ያመኑትንና እነዚያንም ዕውቀትን የተሰጡትን በደረጃዎች ከፍ ያደርጋል። አላህም በምትሰሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው።›› **(አል-ሙጀደላህ:11)**

ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) ይህንን ይላሉ፡-

"አንድ ሰው እውቀትን በመፈለግ ሀሳብ መንገድ ከጀመረ፣ አላህ ወደ ጀነት ከሚወስዱ መንገዶች በአንደኛው ላይ ያኖረዋል። መላዕክቶች በሰውዬው ስለሚደሰቱ ክንፎቻቸውን ይዘረጉለታል። በሰማይና በምድር ያሉ ፍጥረቶች፣ በባህር ውስጥ ያሉ ዓሳዎች ሳይቀሩ ለአዋቂው (ዓሊሙ) ይቅርታ ይለምኑለታል። አንድ ዓሊም ከተርታ አማኞች ዘንድ ያለው ደረጃ ጨረቃ በከዋክብት ላይ እንዳላት ድምቀት ነው። ይህንን ውርስ የተቀበለ በእርግጥ ታላቅ ነገር ተቀበለ" (አቡዳውድ፣ እውቀት 1/3641፣ ቲርሚዚ ዕውቀት 19/2682 ቡኻሪ እውቀት 10፤ ኢብኑ ማጃህ፣ ሙቀዲማህ 17)

"ጥበብ የአማኞች የጠፋች ንብረት ነች። ያገኛት ሰው ይውሰዳት። ከማንም የበለጠ ለርሱም ትገባዋለች።" ቲርሚዚ ፣ ዕውቀት 19/2687፣ ኢብ ማጃህ፣ ተቅዋ 15)

"አንድ አማኝ ጀነት እስኪገባ ድረስ ለዕውቀት ያለው ጥማት አይቋረጥም " (ቲርሚዚ፣ እውቀት 19/2686)

በዚህ ምክንያት ሳይንሳዊ ጥናት በሙስሊሞች ዘንድ እንደ አምልኮ ተግባር የሚቆጠር ነው። በ800 * አህመድ ኢን ነሐዋንዲ ስለ ሥነ ፈለክ ጥናት ጀመረ። ከዚያም ሙስሊሞች ታላላቅ ማዕከላትን መገንባት ጀመሩ። አስትሮላቤ የሚባለውን መሳሪያ በማሻሻል (በማዳበር) የፀሐዩን፣ የከዋክብቱንና የፕላኔቶችን ወርድ መለካት፣ መመተርና ጊዜን መመጠን፣ የተራሮችን ከፍታ፣ የውሃ ጉርጓዶችን ጥልቀት ማወቅ (መለካት) ችለው ነበር። በዚህ ምክንያት ከዚህ ቀደም የነበሩ መመጠኛዎችና ውጤቶች ተከልሰው እንዳዲስ የከዋክብት ምጥን ገላጭ ታሪኮች ተዘጋጅተዋል። አዳዲስ ከዋክብትም ተገኝተዋል። የመሬት የዝማሞትም (ዲግሪ መጠን) እንደገና ተለክቷል፣ ከሌሎች ርጉ ከዋክብት አንፃር የፀሐይ እንቅስቃሴ በግንዛቤ ውስጥ ገብቷል፤ የፕላኔቶችን እንቅስቃሴ በተመለከተ ጠቃሚና አስፈላጊ ግኝቶች ተገኝተዋል።

ሙስሊሞች ሂሳብን በስነፈለግ ጥናት ውስጥ በአዲስ ዘዴ ተጠቅመዋል። "ከቋሚ ሚዛናዊ እንቅስቃሴ" በተሻለ ትሪጎኖሚትሪንና “ሲነስ” የሚባል ስሌት በመጠቀማቸው ወደ ትክክለኛው ልኬት የቀረቡ ውጤቶችን ማግኘት ችለዋል። የፕላኔቶችን እንቅስቃሴ በመለካት ረገድ ታዕምራዊ የሚባሉ ዘዴዎችን መፍጠር ችለዋል።[27]

እንደዚሁም ሁሉ የሥነ ምድርን፣ ሥነ ማዕድን፣ ሥነ ተክል፣ ሥነ ስፍነተ እንሰሳ፣ሂሳብ፣ ፊዚክስ፣ ኬሚስትሪ፣ ህክምና እና ፋርማሲን በተመለከተ አዳዲስ ግኝቶችን ለዓለም ከማስተዋወቃቸው በላይ በነዚህ ሳይንሶች አረዳድና እድገት ላይ አስፈላጊ ግብአቶችን አክለዋል።

ኢብኑ ሲና (980-1037) በ29 የተለያዩ የትምህርት ዘርፎች ላይ ባበረከታቸው አዳዲስ ግኝቶች ለአውሮፓ የሳይንስ መንገድ መቅደድ

[27] Prof. Dr. Seyyid Hüseyin Nasr, *Islamic Science* (Islam vellim), Istanbul 1989, pp. 113-134.

የቻለ ልዩ ዓሊም ነበር፡፡ በሕክምና ላይ የፃፈው "አል-ካኑ ፊ ጢብ" (የህክምና መንገድ) መጽሐፉ ለ600 ዓመታት በአውሮፓውያን ዘንድ ዋና መማሪያ መጽሐፍ ነበር፡፡ በዓይን ውስጥ ያለውን የ"ሬቲናን" አገልግሎት ለመጀመሪያ ጊዜ የጠቀሰው ኢብኑ ሩሽድ (1126-1198) ነበር፡፡ በአስራ አንደኛው መቶ ክፍለ ዘመን የኖረው ዓሊ ቢን ዒሳ በዓይን ላይ የሠራው ስራ "ተዝኪረቱል ካሃላሊን"፣ ለብዙ መቶ ዓመታት የኦፕቲክስ መማሪያ መጽሐፍ የነበረ ሲሆን፣ ወደ ጀርመንኛ፣ ላቲን እና ፈረንሳይኛ ቋንቋ ተመልሷል (ተተርጉሟል)፡፡ ከ9መቶ ዓመታት በፊት የተሳካ የዓይን ሞራ ገፈፋ ቀዶ ጥገና ያደረገው ብቸኛ ሰው አማር ቢን ዓሊ (11 መቶ ክፍለ ዘመን) ነበር፡፡ ስለ ቀዶ ጥገናው በዝርዝር የፃፈበት "አል መንተካብ ፊ ኢላጂል ዓይን" መጽሐፍ ወደ ብዙ የአውሮፓ ቋንቋዎች ተተርጉሟል፡፡ ኢብን ሐይተም (አልሐዝን) (965-1051) የብርሃን (ዋላኒያ Optics) ሳይንስ መስራችና የፊዚክስ ሊቅ ነበር፣ መነፅርን ፈጥሯል፡፡ አሊ ኢብን አባስ (994) የዚህ ዘመንን ሳይንስ ሚያስከነዳ የካንሰር ዕጢን ያስወገደ የተሳካ ቀዶ ጥገና አካሂዷል፡፡ "ኪታቡል ማሊክ" የተሰኘው የህክምና ኢንሳይክሎፒዲያ እስካሁን ድረስ በባለሙያዎች ዘንድ የድማሞት ምንጭ ነው፡፡ ኢብኑል ቃሲም አዝ ዛህራቪ (963-1013) ቀዶ ጥገና ራስን ችሎ (እንድ አንድ ዘርፍ) እንዲቆም ያደረገ ሲሆን፣ "ተስሪፍ" በተባለ መፅሐፍ ለቀዶ ጥገና ሚያገለግሉ 200 ቁሳቁሶችን እንዴትና ለምን እንደሚያገለግሉ በዝርዝር አስፍሯል፡፡ ኢብን አል ነፊስ በ1210 እና በ1288 መካከል የኖረ ሲሆን የመጀመሪያው ስለ ደቂቀ ዝውውር ያገኘ ሲሆን በኢብኑ ሲናን "ካኑን" መፅሐፍ ላይ ትንታኔ ሰጥቷል፡፡

አክሽምሰዲን (1389-1459) "መዳት አል ሐያት" በሚለው መፅሐፍ ስለ በሽታ አምጪ ተህዋሲያን እንዲህ ብሎ ነበር "የሰዎች ህመም አይተላለፍም ብሎ ማሰብ ስህተት ነው፡፡ በሽታዎች ተላላፊዎች ናቸው፡፡ በሽታዎቹን የሚያስተላልፉት በአይን የማይታዩ ሕይወት ያላቸው ዘሮች ናቸው፡፡"

ኻሪዝሚ (780-850) ለመጀመሪያ ጊዜ ዜሮን የተጠቀመና የአልጀብራን መሠረት የጣለ ሲሆን መፅሐፉንም በርሱ ስም "አል ጃቢር ወል ሙቀበል" ብሎ ሰይሞታል፡፡ የሙሳ ልጅ (9 መቶ ክፍለ ዘመን) የምድራችንን መጠነ ዙሪያ የለካ ሲሆን ውጤቱ ከአሁን ዘመን ውጤት ጋር ልዩነቱ እጅግ በጣም ትንሽ ነበር፡፡ በይሩኒ (973-1051) በተለያዩ መስኮቶች ላይ አዳዲስ ግኝቶችን ያገኘ ሲሆን ምድር በራሷ እና በፀሐይ ዙሪያ እንደምትዞር ለመጀመሪያ ጊዜ ያሳወቀ ነበር፡፡ በተጨማሪም በህንድ ሄንደን በተሰኘ ከተማ ባካሄደው ጥናት የምድራችንን ስፋት በትክክል ለክቷል፡፡ የተጠቀመበት ቀመር (ፎርሙላ) በአውሮፓ "የበይሩኒ ፎርሙላ" በመባል ይታወቃል፡፡ ባታኒ (አል ባተኚ) የፀሐይን መጠነ ዓመት በ24 ሰዓት ልዩነት ስህተት ሊለካ ችሏል፡፡ ኢስማኤል ጃህዋሪ (950-1010) ለመብረር የሞከረ የመጀመሪው ሰው ነበር፡፡ ኢብን ፊርናስ በ880 የራሱን አውሮፕላን የሰራ ሲሆን በወፍ ላባና በጨርቅ በሰራው አውሮፕላን ለረጅም ሰዓት በዓየር ላይ ከመቆየቱም በላይ በተሳካም ሁኔታ አርፏል፡፡ ራዚ (864-925) ስለ መሬት ስበት (Gravity) አውስቷል፡፡ ክርስቶፎል ኮሎምቦስ (1446-1506) ስለአሜሪካ መኖር ከሙስሊሞች እንዳወቀ የኢብን ሩሽድን (1126-1198) መጽሐፍት በተለየ ጠቅሶ ተናግሯል፡፡ ኢድሪሲ (1100-1166) ከአሁን ዘመን የዓለም ካርታ ጋር የሚመሳሰል የዓለማችንን ካርታ ከ800 ዓመታት በፊት ስሎ ነበር፡፡[28]

በተለያዩ ቦታዎችና ጊዜያት የተለያዩ ስልጣኔዎች ብቅ ብለዋል፡፡ አንዱ ስልጣኔ ከሌላው እየተዋሰ፣ በሌላውም ላይ ተፅዕኖ እያሳደረ ሳይንስን አሳድጓል፡፡ ሙስሊሞችም ከቀዳሚዎቹ የስልጣኔ ዕውቀቶች

[28] እንደ ምንጭና ሌሎች ምሳሌዎችን ለማየት **Prof. Dr. Fuat Sezgin,** *Science et technique en Islam I-V,* Frankfurt, 2004 (*Islam'da Bilim ve Teknik I-V,* Ankara 2007) and his other books; **Prof. Dr. Seyyid Hüseyn Nasr,** *Islamic Science, An Illustrated Study,* World of Islam Festival Pub. Co. Ltf., England, 1976 (*Islam ve Ilim*, Istanbul 1989); **Dr. Sigrid Hunke,** Allahs Sone über dem Abendland-Unser Arabischen Erbe, Germany 1960; **Carra de Vaux,** *Les Penseurs de l'Islam,* Paris 1923; *Avicenne,* Paris 1900; **Prof. Dr. Mehmet Bayraktar,** *Islâm'da Bilim ve Teknoloji Tarihi (The History of Science and Technology in Islam),* Ankara 1985; **Şaban Doğen,** *Muslüman Ilim ضncüleri Ansiklopedisi (The Encyclopedia of Muslim Pioneers of Science),* Istanbul 1987; http://www.**1001inventions**.com.

ተጠቅመዋል፡፡ ይህንንም በፍፁም ትህትና አሳውቀዋል፡፡ የተቀበሉትንም ሳይንስ አዳብረውና አሻሽለው ለቀጣዩ አሳልፈዋል፡፡ የቀደምት ስልጣኔዎች ውጤት የሆኑ መፅሐፍት ሙስሊም ምሁራን የተረጎሙዋቸው ሲሆን ሲተረጉሙ ግን እየመረጡ ነበር፡፡

## ፍትህ፣ ተቀዳሚው ዕሴት

አላህ ፍፁም ፍትሃዊ ነው፡፡ በምንም መልኩ ፍትህ አያጓድልም፡፡ እርሱ ካሉት ውብ መጠሪያዎች መካከል "አል-አድል" (ፍጹም ፍትሀዊ) የሚለው አንደኛው ነው፡፡[29]

በዚህ ምክንያት እኛም ባሪያዎቹ ፍትሃዊ እና ጻድቅ እንድንሆን ይፈልጋል፡፡ አላህ (ሱ.ወ) በቅዱስ ቃሉ እንዲህ ይላል፡፡

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ كُونُوا۟ قَوَّٰمِينَ بِٱلْقِسْطِ شُهَدَآءَ لِلَّهِ وَلَوْ عَلَىٰٓ أَنفُسِكُمْ أَوِ ٱلْوَٰلِدَيْنِ وَٱلْأَقْرَبِينَ ۚ ﴿١٣٥﴾ ﴾ النساء: ١٣٥

‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ! በትክክል (ፍትሕ) ቀዋሚዎች በነፈሶቻችሁ ወይም በወላጆችና በቅርብ ዘመዶች ላይ ቢኾንም እንኳ ለአላህ መስካሪዎች ኹኑ፡፡ ፡››
**(አል ኒሳእ፡ 135)**

ሙስሊሞች በጠላቶቻቸው ላይ እንኳን ፍትህ እንዳያጓድሉ ያዛል፡፡

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُوا۟ كُونُوا۟ قَوَّٰمِينَ لِلَّهِ شُهَدَآءَ بِٱلْقِسْطِ ۖ وَلَا يَجْرِمَنَّكُمْ شَنَـَٔانُ قَوْمٍ عَلَىٰٓ أَلَّا تَعْدِلُوا۟ ۚ ٱعْدِلُوا۟ هُوَ أَقْرَبُ لِلتَّقْوَىٰ ۖ وَٱتَّقُوا۟ ٱللَّهَ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ خَبِيرٌۢ بِمَا تَعْمَلُونَ ﴿٨﴾ ﴾ المائدة: ٨

‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ለአላህ ቀጥተኞች በትክክል መስካሪዎች ኹኑ፡፡ ሕዝቦችንም መጥላት ባለማስተካከል ላይ አይገፋፋችሁ፡፡ አስተካክሉ፡፡ እርሱ (ማስተካከል) ለአላህ ፍራቻ በጣም የቀረበ ነው፡፡ አላህንም ፍሩ፡፡ አላህ በምትሠሩት ሁሉ ውስጠ ዐዋቂ ነው፡፡›› **(አል ማዒዳህ 5፡8)**

[29] Tirmizî, Deavât, 82/3507.

ነብዩም (ሰ.0.ወ) በመልካም ሆነ በመከራ፣ በሰላም ሆነ በጦርነት (ንዴት) ጊዜያት ፍትህ እንዳናጓድል መክረዋል፡፡ ይህንንም መርህ የተከተሉ የበዛ ምንዳ እንደሚሰጣቸው አብስረዋል፡፡

*መሠረታዊው የኢስላም ዲያሌክቲክ ወይም ተቃርኖሽ በጨቋኞችና ጨቋኞችን በሚደግፉ እና በፍትሃዊያን እና ፍትህን በሚያቀነቅኑ መካከል ያለው ትግል ነው፡፡*[30]

ቅዱስ ቁርዓን" እንዲህ ይላል"

قَالَ تَعَالَىٰ: أَعُوذُ بِاللَّهِ مِنَ الشَّيْطَانِ الرَّجِيمِ ﴿ فَإِنِ انتَهَوْا فَإِنَّ اللَّهَ غَفُورٌ رَّحِيمٌ ﴿١٩٢﴾ ﴾ البقرة:
١٩٢

"ቢከለከሉም አላህ መሓሪ አዛኝ ነው፡፡" **(አልበቀራህ፡ 192)**

*ሙስሊሞች የሰዎችን ሰብዓዊ መብት ከሚያከብር ፍትሃዊ ከሆነ ሙስሊም ሆነ ሙስሊም ካልሆነ ጋር መኖር ይችላሉ፡፡*[31] *ሆኖም ሙስሊም ሆኖ እንኳ የሰዎችን ሰብዓዊ መብት ከማያከብር ኢ ፍትሃዊ ጋር መኗኗር ሳይሆን መቃወም ግዴታ ይሆናል፡፡ ስለዚህ በህብረተሰብ ደረጃ ያለው "የእኛ" እና "እነሱ" መለያ መስፈርቱ ጭቆናና ፍትህ ነው፡፡* [32]

በዚህ ምክንያትሙስሊሙ ማህበረሰብ ለፍትህ ከፍተኛ አትኩሮት ይሰጣል፡፡ የሚከተለው ታሪክ ለዚህ ማሳያ ይሆነናል፡፡ ሙስሊሞች የሶሪያዊቷን "ሂምስ" ከተማ ይቆጣጠራሉ፡፡ የነዋሪዎቹን ሁለንተናዊ ደህንነት እያስጠበቁ ስለነበር ምክንያታዊ ታክስ ይሰበስባሉ፡፡ የባዘንታይኑ ንጉስ ሄራክለተስ ሙስሊሞችን ለመዋጋት ወደ የርሙክ ይንቀሳቀሳል፡፡ በጦሩ ግዙፍነት ሀሳብ የገባቸው ሙስሊሞች ከሂምስ ህዝቦች የሰበሰቡትን ታክስ "እኛን ለማጥቃት የተንቀሳቀሰ ግዙፍ ጦር ስላለ፤

---

30 Heysemî, I, 90; Ebû Nuaym, *Hilye,* II, 343; VI, 268-9.

31 Al-Baqara (The Cow), 2: 192.

32 Prof. Dr. Recep Şentürk, *İnsan Hakları ve İslâm (Human Rights and Islam)*, p. 22.

እናንተን ምንጠብቅበት አቅም የለንም። ስለዚህ ከኛ በምታደርጉት ነገር ነፃ ናችሁ፤ ያሻችሁንም ርምጃ ውሰዱ" ብለው ይመልሳሉ።

የሂምስ ሰዎችም "በአላህ እንምላለን፣ የእናንተ አመራር ሥር ሆነን ከተማችንን ከሄራክለስ እንጠብቃታለን" አሉ። አይሁዶችም "በተውራት እንምላለን! ሄራክለተስ እኛን ካላሸነፈንና ካላጠፋን ወደ ከተማዋ አይገባም" ሲሉ ዛቱ። የከተማይቷን በሮች በመከርቸም ከጠላት ወረራ ጠበቋት። ሙስሊሞቹ የሰላም ስምምነት የተፈራረሙዋቸው  የሌሎች ከተሞች ክርስቲያኖች እና አይሁዶች ተመሳሳይ ነገር ነበር ያደረጉት። "ሮማዎቹ ሙስሊሞችን ካሸነፉ ወደ ቀድሞው የጭቆናና አምባገነን አገዛዝ መመለሳችን ነው። ብዙ መከራዎችም መምጣታቸው ነው። ሙስሊሞች ይህንን ጦርነት ቢያሸንፉና በስምምነታችን መሠረት ወደ ቀድሞው ትብብራችን በተመለስን እንመኛለን" ብለው ነበር።[33]

[33] Belâzurî, *Fütûhu'l-büldân,* Beirut 1987, p. 187.

## ኢስላም ዓለማቀፋዊ ኃይማኖት

ኢስላም ሰዎችን ብቻ ሳይሆን አጋንቶችንም ወደ ብርሀን ይጣራል፡፡[34] ዘሩ፣ ቀለሙ፣ ፆታው፣ ወይም ብሔራዊ ማንነቱ ሳይመነዘር ሁሉም ሰው ሙስሊም መሆን ይችላል፡፡ ኢስላም ሰዎችን በኃላፊነታቸውና መብታቸው አንፃር ስለሚመለከታቸው ህዝቦች በሁለት ብቻ ነው የሚከፈሉት አማኝና አማኝ ያልሆኑ፡፡[35]

ለሰው ዘር በሙሉ ደህንነትና ደስታ አዛኝነቱ ሁሉን ባካበበው አላህ የተላከ ኃይማኖት በጥቂት ሰዎች ቁጥጥር ሥር እንዲገባ መፍቀድ ትክክል አይደለም፡፡ ይህ ከአላህ (ሱ.ወ) እዝነትና ርህራሄ አንፃር የሚታይ ነው፡፡[36] የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲህ ይላሉ፡፡

"አላህ (ሱ.ወ) ለሌሎች ለሚያዝኑ ያዝናል፡፡ (ስለዚህ) በምድር ላይ ላሉ በሙሉ እዘኑ በሠማይ ያለው እንዲያዝንላችሁ፡፡" (አቡ ዳውድ፣ አዩብ፣ 58/4941፤ቲርሚዚ፣ቢር 16/1914) አህመድቢን ሐንበል ፷፷(60)

ይህ ሐዲስ ስለተወሠኑ ዘሮች አይናገርም፡፡ "ሙስሊሞችንም" ብቻ አይመለከትም፡፡ በአጠቃላይ ለሰው ዘር፣ ለእንስሶችና ተክሎች በሙሉ አዛኝ እንድንሆን የሚያዝ ነው፡፡

ቅዱስ ቁርአን ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) የሰውን ዘር በሙሉ እንዴት መጣራት እንዳለባቸው ሲገልፅ

---

34 Translator's note: Islam acknowledges the existence of these creatures and that they have free will.

35 Every human is the nation of the Prophet of his time. All people after HE Muhammad had been sent as a Prophet
are considered as his nation. However, while some believe
his Prophethood, others deny it.

36 Translator's note: *Rahman* is interpreted as the All- Merciful in the sense that Allah's mercy encompasses allcreation in the universe, while *Raheem* is interpreted as Allah's mercy for the believers in the Hereafter.

قَالَ تَعَالَى: أَعُوذُ بِاللَّهِ مِنَ الشَّيْطَانِ الرَّجِيمِ ﴿ قُلْ يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ إِنِّى رَسُولُ ٱللَّهِ إِلَيْكُمْ
جَمِيعًا ٱلَّذِى لَهُۥ مُلْكُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ ۖ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا هُوَ يُحْىِۦ وَيُمِيتُ ۖ فَـَٔامِنُوا۟ بِٱللَّهِ
وَرَسُولِهِ ٱلنَّبِىِّ ٱلْأُمِّىِّ ٱلَّذِى يُؤْمِنُ بِٱللَّهِ وَكَلِمَٰتِهِۦ وَٱتَّبِعُوهُ لَعَلَّكُمْ
تَهْتَدُونَ ﴿١٥٨﴾ ﴾ الأعراف: ١٥٨

"(ሙሐመድ ሆይ!) በላቸው እናንተ ሰዎች ሆይ! እኔ ወደናንተ ወደ ሁላችሁም የአላህን መልዕክተኛ ነኝ፤ (እርሱም) ያ የሰማያትንና የምድር ንግስና ለርሱ ብቻ ነው የሆነ ነው፡፡ "(ሙሐመድ ሆይ!) ለአለማትም እዝነት አድርገን አንጂ አልላክንህም፡፡" **(አል-አዕራፍ፡ 158)**

﴿ وَمَآ أَرْسَلْنَٰكَ إِلَّا رَحْمَةً لِّلْعَٰلَمِينَ ﴿١٠٧﴾ ﴾ الأنبياء: ١٠٧

‹‹(ሙሐመድ ሆይ!) ለዓለማትም እዝነት አድርገን እንጅ አልላክንህም፡፡››

**(አል-አንቢያ፡ 107)**

በዚህ ምክንያት ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ) አረቦችን ብቻ ሳይሆን ባዛንታይኖችን (ምስራቅ ሮማውያን)፤ አቢሲኒያውያንን፣ ግብፃውያንን እና በርሳቸው ዘመን የነበሩትን ንጉሶችና አዜዎች ደብዳቤ በመላክ ወደ ኢስላም ጠርተዋል፡፡[37]

በተጨማሪም ኢስላም የጊዜም ሆነ ቦታ ውስንነት የለውም፡፡ በጊዜም ሆነ ድንበር ወሰን አልተከበበም፡፡ ይህንን ዕውነታ በሐጅ ወቅት መመልከት ይቻላል፡፡ ከተለያዩ ሃገራት የመጡ ሙስሊሞች ፍጹም በሆነ ወንድማማችነትና እኩልነት በመካ ይሰበሰባሉ፡፡

ኢስላም የሰውን ልጅ ፍላጎቶች የሚያሟላ አወቃቀር ያለው ነው፡፡ ኢስላም የሰውን ልጆች መንፈሳዊ፣ አካላዊና ማህበራዊ መብት የሚያሟላ፤ ሌሎች እምነቶች ፈፅሞ ምሉዕ እና አጥጋቢ መልስ መስጠት ላልቻሉባቸው ጉዳዮች፣ ማለትም በሕይወትና ሞት፣ በአምላክነት ፣ነብያት፣ መላዕክት፣ ሰይጣን፣ ይህንን ዓለም፣ መጪው

[37] While the texts of these letters are available, the originals of some of them can be seen in Istanbul Topkapi Pala

ዓለም፣ ምንዳና ቅጣት፣ ገነትና ገሃነም፣ ምሉዕና አጥጋቢ ምላሽ የሰጠ የዕምነትና ሕይወት ስርአት ነው፡፡

ስለዚህ ጉዳይ የበለጠ ለመረዳት የሚከተለውን ማስታወስ በቂ ነው፡- ቅዱስ ቁርዓን ሙስሊሞች በጨቋኞችና አምባገነኖች ሥር ሆነውም ሆነ ከአትላንቲክ ውቅያኖስ እስከ ሰላማዊ ውቅያኖስ ያካለለ አመራር ባለቤት በሆኑበት ወቅት የሙስሊሞችን ጥያቄዎች መልሷል፡፡ ፍላጎታቸውን አሟልቷል፡፡ ይህ ማህበረሰብ (ሙስሊሙ) የእምነቱን ምንነት ለመረዳት፣ የሚፈልጋቸውን የአምልኮ ስርዓቶች ለመገንዘብ፣ ማህበራዊ ህይወቱ፣ ሕግጋቱ እና ሌሎችም ሊያሟላቸው የሚፈልጋቸውን ፍላጎቶች ከዚህ መለኮታዊ መጽሐፍ፣ ከቅዱስ ቁርአን ቀድቷል፡፡[38]

## የሰው ልጅ እኩልነት

በኢስላም የሰዎች ታላቅነት ሚለካው ግልፅ በሆነና ሰዎች ምርጫ በሌላቸው ነገሮች- ዘር፣ ቀለም ወይም የብሄር ማንነት - ሳይሆን ሰዎች በምርጫቸው፣ በትጋትና በልፋት በሚያገኙት የአላህ ቀረቤታ ነው፡፡ ኃብት፣ ውበት፣ ጥንካሬ ወይም ስልጣን የታላቅነት መለኪያ አይደሉም፡፡ እነዚህ በአላህ የሚሰጡና ለመልካም ጉዳዮች በማዋል አመስጋኝነታችንን የምናሳይባቸው ነገሮች ናቸው፡፡

የሰው ልጆች በዚህ ምድር ላይ የሚሰጧቸው ስጦታዎች ለተማሪ እንደሚቀርቡ ጥያቄዎች ናቸው፡፡ በሚቀርብለት ጥያቄ የሚኩራራ ተማሪ የለም፡፡ የተማሪው ደስታ የሚመነጨው ጥያቄዎቹን በመመለስ በሚያገኘው ጥሩ ውጤት ነው፡፡ በአኼራ ስኬት እንድናገኝበት የተሰጡን ሥጦታዎች በአግባቡ ተጠቅመንባቸው እንደሆነና እንዳልሆነ ውጤቱን የምናየው በአኼራ ስለሆነ፣ በሰራነው መልካም ሥራ የምትጫረዋ ኩራት ወደ ሌላ ሳትሰደድ እንድትከስም ይሆናል፡፡ ከዚህ በተቃራኒው በኩራት ብትወጠር መጨረሻው ጥፋት ነው፡፡ ስለሆነም ታላቁ የኢስላም

38 M. Hamidullah, *Kur'ân-ı Kerîm Tarihi (The History of the Noble Quran)* (Introduction Section of *Le Saint Coran*), p. 23.

ዓሊም አቡ ሀዚም እንዳሉት "ወደ አላህ የማያቃርብ የትኛውም አይነት ሃብት (ንብረት) ችግር ነው።"

ምንም እንኳን ታላቁ ነብይ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የተላኩት ለዓለማት እዝነት ቢሆንም ከሰዎች በላይ ያላቸውን ደረጃ ሲገልጹ "ኩራት የለም (አልኮራም)" የምትለዋን ሐረግ ብዙ ጊዜ ይደጋግሟት ነበር።[39]

በአላህ ፊት ኃላፊነቱን የሚያውቅና ግዴታውን የሚወጣ አማኝ ከቸልተኛው በእጅጉ የበለጠ ነው።[40] ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በመሠናበቻ ንግግራቸው አስረግጠው የተናገሩትም ይህንን ነው።

"ሰዎች ሆይ! ልብ አድርጉ፤ አምላካችሁ አንድ ነው። አባታችሁ (አደም) አንድ ነው። ተጠንቀቁ! አረቡ አረብ ካልሆነው በምንም አይበልጥም፤ አረብ ያልሆነውም ከአረቡ እንዲሁ በምንም አይበልጥም፤ ነጩም ከጥቁሩ፤ ጥቁሩም ከነጩ አይበልጥም። አንዳችሁ ካንዳችሁ የምትበላለጡት በተቅዋ ብቻ ነው።" (አህመድ ኢብን ሐንበል 4:411)

## የኃይማኖትና የህሊና ነፃነት

አላህ (ሱ.ወ) ለሰዎች መልካሙንና ክፋውን ያሳያቸው ቢሆንም ያሻቸውን እንዲመርጡ ነፃ አድርጎ ፈጥሯቸዋል። በምርጫቸው አይገባም። ሁሉም ሰው ያሻውን የመምረጥ መብት እንዳለው ሁሉ የምርጫውን ውጤት የመቀበል ኃላፊነትም አለበት። ቅዱስ ቁርአን እንዲህ ይላል።

﴿وَلَوْ شَآءَ رَبُّكَ لَآمَنَ مَن فِي ٱلْأَرْضِ كُلُّهُمْ جَمِيعًاۚ أَفَأَنتَ تُكْرِهُ ٱلنَّاسَ حَتَّىٰ يَكُونُوا۟ مُؤْمِنِينَ ٩٩﴾ يونس: ٩٩

‹‹ጌታህም በሻ ኖሮ በምድር ያሉት ሰዎች ሁሉም የተሰበሰቡ ሆነው ባመኑ ነበር። ታዲያ አንተ ሰዎችን አማኞች እንዲኾኑ ታስገድዳለህን?›› **(ዩኑስ፡ 99)**

---

39 Tirmizî, Menâkıb, 1/3616; Dârimî, Mukaddime, 8.

40 Al Hujurat (The Private Quarters), 49: 13.

﴿ وَقُلِ ٱلْحَقُّ مِن رَّبِّكُمْ فَمَن شَآءَ فَلْيُؤْمِن وَمَن شَآءَ فَلْيَكْفُرْ ﴾ الكهف: ٢٩

«እውነቱም ከጌታችሁ ነው፡፡ የሻም ሰው ይመን፤ የሻም ሰው ይካድ» በላቸው፡፡›
**(አል-ካህፍ፡ 29)**

﴿ إِن تَكْفُرُوا۟ فَإِنَّ ٱللَّهَ غَنِىٌّ عَنكُمْ وَلَا يَرْضَىٰ لِعِبَادِهِ ٱلْكُفْرَ وَإِن تَشْكُرُوا۟ يَرْضَهُ لَكُمْ وَلَا تَزِرُ وَازِرَةٌ وِزْرَ أُخْرَىٰ ثُمَّ إِلَىٰ رَبِّكُم مَّرْجِعُكُمْ فَيُنَبِّئُكُم بِمَا كُنتُمْ تَعْمَلُونَ إِنَّهُۥ عَلِيمٌۢ بِذَاتِ ٱلصُّدُورِ ﴿٧﴾ ﴾ الزمر: ٧

‹‹ብትክዱ አላህ ከእናንተ የተብቃቃ ነው፡፡ ለባሪያዎቹም ክህደትን አይወድም፡፡ ብታመሰግኑም፤ እርሱን ይወድላችኋል፡፡ ማንኛይቱም ኃጢኣትን ተሸካሚ ነፍስ የሌላይቱን ኃጢኣት አትሸከምም፡፡ ከዚያም መመለሻችሁ ወደ ጌታችሁ ነው፡፡ ትሠሩት የነበራችሁትንም ይነግራችኋል፡፡ እርሱ በልቦች ውስጥ ያሉትን ዐዋቂ ነውና፡፡›› **(አዝ-ዙመር :7)**

በጃህሊያ ዘመን ልጆቻቸው በጠና የታመሙ እናቶች "ልጄ በህይወት ከቆየልኝ አይሁድ አደርገዋለሁ" እያሉ ይሳሉ ነበር፡፡ በዚህም ምክንያት የበኑ ነድር የአይሁድ ነገዶች ከነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ጋር የተጋቡትን ቃል በማፍረሳቸው ከመዲና ሲባረሩ፤ ከነርሱ ውስጥ በዚህ ስላት ምክንያት አይሁዳዊ የሆኑ ልጆች ነበሩ፡፡ የነዚህ ልጆች ሙስሊም ዘመዶች "ልጆቻችንን አንሰጥም" (በሃይል እናስቀራቸዋለን፡፡ ሙስሊምም እናደርጋቸዋልን) ብለው ነበር፡፡ አላህ ግን፡- በኃይማኖት ማስገደድ የለም"[41] የምትለዋን አንቀፅ አወረደ፡፡

ኢስላም በግድ የሚቀበሉት ኃይማኖት አይደለም፡፡ ስለሆነም የትኛውንም ዓይነት እምነቱን ሰዎች ላይ የመጫን አካሄድን አይቀበልም፡፡ በራሱም ላይ እንዲመጣ አይፈልግም፡፡ አላህ ቅዱስ ቁርአንን የመጠበቁ አንደኛው መገለጫም ይኼው ነው፡፡ ሰዎች ኃይማኖቱን በጭንቅላታቸው አመዛዝነው እንዲቀበሉትም በማሰብ፡፡ ታዕምራት ኃይማኖቱን በመስበክ ሆነ በማስፋፋት ረገድ ቦታ የላቸውም፡፡ ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ) እንግዳ ክስተት

[41] Al Baqara (The Cow), 2: 256. Abu Dawud, Jehad, 116/2682; Vâhidî, pp. 85-87.

እንዲያደርጉ ሰዎች ሲጠይቋቸው፣ ጥያቄያቸው ተቀባይነት ያጣው ለዚህ ነው። ኢስላም ሰዎች ባደጉበትና በበሰሉበት ጊዜ የተገለጠ ስለሆነ የቁርዓን ተዓምር የሰዎችን አቅል በማናገሩ ላይ ነው። ሰዎችን እንደ ማግኔት ሚስበው በምክንያታዊነት ህግና አሳማኝ መረጃዎችን በማቅረብ ነው። ስለዚህ ኢስላም ሰዎች እንዲሰልሙ ኃይል ይጠቀማል ማለት የማይታመን ነው።

ታዋቂው እንግሊዛዊ የታሪክ ምሁር ፊሊፕ ማርሻል ብራውን (Philip Marshall Brown) ሲፅፍ "ቱርኮች ታላላቅ ድሎችን ቢጎናፀፉም፣ በቁጥጥራቸው ስር ያዋሉዋቸውን ሃገራት እንደባህላቸውና ልምዳቸው ራሳቸውን በራሳቸው እንዲያስተዳድሩ ይፈቅዱላቸው ነበር።" ብሏል።

ናፖሊን ቦናፓርቴ ከ1798-1799 ባሉት ዓመታት የኦቶማን ኤምባየርን ሲያጠቃ በፍልስጤምና በሶሪያ ያሉ አርመኞች እንዲያምጹ ፈልጎ ነበር። በኢስታንቡል የፈረንሳይ አንባሳደር ሰባስትያኒ የሚከተለውን መልስ ለናፖሊን ልኮለት ነበር - "በቱርኮች አገዛዝ ስር ያሉ አርመኞች በኑሮዋቸው እጅግ ስለተመቻቸው እነርሱን እንዲያምፁ ማድረግ ፈፅሞ አይቻልም"[42]

## ኢስላም ለመገንዘብ ሆነ ለአተገባበር ገር ነው

የእዝነቱ ሥፋትና ጥልቀት የማይታወቀው ጌታችን የኢስላምን እያንዳንዱ ገፅታ ለመረዳትም ሆነ ለአተገባበር ምቹ፣ ለባሪያው ገር አድርጎታል። አላህ (ሱ.ወ) በቅዱስ ቃሉ፡-

﴿ لَا يُكَلِّفُ ٱللَّهُ نَفْسًا إِلَّا وُسْعَهَا ۚ لَهَا مَا كَسَبَتْ وَعَلَيْهَا مَا ٱكْتَسَبَتْ ۗ رَبَّنَا ﴿٢٨٦﴾ ﴾
البقرة: ٢٨٦

‹‹አላህ ነፍስን ከችሎታዋ በላይ አያስገድዳትም። ለርስዋ የሠራችው አላት። በርስዋም ላይ ያፈራችው (ኀጢአት) አለባት።›› **(በቀራህ፡ 286)**

42 See http//www.atmg.org/ArmenianProblem.html.

﴿ يُرِيدُ ٱللَّهُ بِكُمُ ٱلْيُسْرَ وَلَا يُرِيدُ بِكُمُ ٱلْعُسْرَ ﴾ البقرة: ١٨٥

‹‹አላህ በእናንተ ገሩን (ነገር) ይሻል፡፡ በእናንተም ችግሩን አይሻም፡፡››

**(በቀራህ፡ 185)**

﴿ وَجَٰهِدُواْ فِي ٱللَّهِ حَقَّ جِهَادِهِۦۚ هُوَ ٱجْتَبَىٰكُمْ وَمَا جَعَلَ عَلَيْكُمْ فِي ٱلدِّينِ مِنْ حَرَجٍ ﴾ الحج: ٧٨

‹‹በአላህም ሃይማኖት ተገቢውን ትግል ታገሉ፡፡ እርሱ መርጧችኋል፡፡ በናንተም ላይ በሃይማኖቱ ውስጥ ምንም ችግር አላደረገባችሁም፡፡››

**(አል-ሐጅ፡ 78)**

﴿ يُرِيدُ ٱللَّهُ أَن يُخَفِّفَ عَنكُمْۚ وَخُلِقَ ٱلْإِنسَٰنُ ضَعِيفًا ۝٢٨ ﴾ النساء: ٢٨

‹‹አላህ ከእናንተ ሊያቃልልላችሁ ይሻል፡፡ ሰውም ደካማ ኾኖ ተፈጠረ፡፡››

**(አል ኒሳዕ 4:28)**

ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) ይህን የኢስላም ገፅታ እንዲህ አድርገው ገልፀውታል፡፡

"አላህ (ሱ.ወ) መላዕክቶቹን እንዲህ ሲል አዘዛቸው፡- "ባሪያዬ ወንጀል ለመስራት ቢፈልግ ወንጀሉን እስኪሰራው ድረስ ምንም አትመዝግቡ፡፡ ወንጀሉን ከሰራው እንደ አንድ ኃጢያት መዝግቡ፡፡ ለእኔ ብሎ ከወንጀሉ ሲታቀብ ምንዳ ፃፉለት፡፡ ባሪያዬ መልካም ነገር አስቦ ባይፈፅመው እንኳን እንደሰራው አድርጋችሁ መዝግቡለት፡፡›› ነገር ግን ያሰበውን መልካም ነገር ከሠራ ከአስር እጥፍ ጀምራችሁ እስከ ሰባት መቶ እጥፍ ድረስ አስቡና መዝግቡለት፡፡ (ቡኻሪና፣ ተውሂድ፣ 35፤ሙስሊም፣ ኢማን፣203.205)

የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ጓደኞች እንደሚናገሩት ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ቀና ሰው፣ ለመቅረብ የማይከብዱ፣ ለሰዎችም ቀላልን የሚመቹ እንደነበሩ ይናገራሉ፡፡[43]

[43] Muslim, Hajj, 137.

ኢስላም ገራገር ኃይማኖት እንደሆነ የሚያሳዩ ውስን ምሳሌዎችን እንጥቀስ፡-

- በኢስላም ሰው የሚጠየቀው ማድረግ በሚችለው ነገር ላይ ብቻ ነው፡፡ ከአቅሙ በላይ የሆኑ ነገሮችን እንዲሸከም (ኃላፊነትን እንዲወስድ)፤ እንዲሁም ተገዶ ወይም ከአቅም በላይ በሆኑ ሁኔታዎች ውስጥ ለሚፈፅመው ድርጊት አይጠየቅም፡፡

- በኢስላም ሂደታዊ ለውጥ ወሳኝ ነው፡፡ አስካሪ መጠጥ፣ አራጣ (ወለድ) እና ዝሙት የተከለከሉት ሶስትና አራት አመታት በፈጀ ሂደት ነው፡፡

- ከሶላት በፊት ውዱዕ በውሃ ማድረግ ግዴታ ነው፡፡ ነገር ግን ውሃ በሌለበትና በውሃ አማካኝነት የሚመጣ አካል ጉዳት ካለ ተየሙም (በዓፈር) ማድረግ ይቻላል፡፡

- መንገደኞች ከሱብሂ በስተቀር ያሉትን ተከታታይ ሁለት የሶላት ወቅቶች በማጣመር ባለ አራት ረከዓ ሶላቶችን ወደ ሁለት ቀንሰው መስገድ ይችላሉ፡፡

- ቆሞ መስገድ ይልቻለ ቁጭ ብሎ፣ ቁጭ ብሎ ያልቻለ ተጋድሞ፣ ተጋድሞ ካልተቻለ በአይን ጥቅሻ መስገድ ይችላል፡፡

- ሶላትን ለመስገድ በአቅራቢያ መስጊድ ከሌለ ንፁህ ቦታ ላይ መስገድ ይችላል፡፡ ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ) እንዳሉት "ምድር ሁሉ ለመስገጃነት ንፁህ ተደርጋልኛለች፡፡ የኔ ዑመት የሆነ በሙሉ የሶላት ወቅት እንደገባ ባገኘበት ቦታ ይስገድ" (ቡኻሪ፣ተይሙም 1)

- ፆም ሕመምተኛ እና መንገደኛ ለሆኑ ሊከብድ ይችላል፡፡ በዚህ ምክንያት እነዚህ ሰዎች የረመዳንን ፆም እንዲፆሙ አይገደዱም፡፡ ከህመማቸው ሲሻላቸው ወይም ከሄዱበት ሲመለሱ ወይም በሄዱበት ሲመቻቸው ያለፋቸውን ፆም መተካት ይችላሉ፡፡

- ሐጅ ለማድረግ ያሰበ በተለያዩ ምክንያቶች የደህንነት ችግር በመንገድ ላይ ካለ፣ ይህ የደህንነት ችግር እስኪወገድ ሐጁን ሊያቆየው ይችላል፡፡

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲህ ብለዋል፡- "ኢስላምን ገር ያደረገው አላህ ምስጋና ይድረሰው!" ብለዋል፡፡ (አህመድ ኢብን ሐንበል 6፡167)

## ኢስላም ብሩህነትንና ተስፋን በሰዎች ውስጥ እንዲሰርፅ ያደርጋል

ኢስላም ሰዎች ብሩህ እንዲሆኑ ይሻል፡፡ አላህ (ሱ.ወ) "እዝነቴ በሁሉም ነው" ብሎ በራሱ ላይ ግዴታ አድርጓል፡፡[44] የአላህም መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) "አላህ (ሱ.ወ) ሁሉንም ፍጥረቱን ሲፈጥር ከዙፋኑ አጠገብ ባለው መፅሐፍ "እዝነቴ ቁጣዬን አካብቦታል - ሲል ፅፏል" ብለዋል፡፡ (ቡኻሪ፣ተውሂድ፣15)

ይህ ብቻ ሙስሊሞች ተስፈኛ እንዲሆኑ ያደርጋቸዋል፡፡ የሙስሊምን ኑሮ (ሕይወት) ምቹ ከሚያደርጉ ተጨማሪ ነገሮች ይቅር ባይነት፣ እዝነት፣ ትዕግሥት፣ ተወኩል (በአላህ ላይ መመካት)፣ ፍጹም ታዛዥነት፣ ሁኔታዎችን መቀበልና ለሰዎች (ስለሰዎች) መልካም ማሰብ ይጠቀሳሉ፡፡ ችግርና መከራ የኃጢያት ማራገፊያ እና መንፈሳዊነትን ማጎልበቻ ናቸው የሚለው የሙስሊሞች እምነት የህይወትን ፈተናና ሸክም በእጅጉ ያቃልላል፡፡ ነገሮችን ለመለወጥ ያቅሙን ያህል የተፍጨረጨረና ውጤቱን ለአላህ የሰጠ ሙስሊም ሐዘንተኛ ይሆናል ማለት ዘበት ነው፡፡ እንዲህ አይነት ሙስሊም ፍፁም ርጉና በፍሰሃ ዓለም ውስጥ የሚኖር ነው፡፡ አላህ (ሱ.ወ) እንዲህ ይላል፡-

﴿ قُلْ يَٰعِبَادِىَ ٱلَّذِينَ أَسْرَفُوا۟ عَلَىٰٓ أَنفُسِهِمْ لَا تَقْنَطُوا۟ مِن رَّحْمَةِ ٱللَّهِ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ يَغْفِرُ ٱلذُّنُوبَ جَمِيعًا ۚ إِنَّهُۥ هُوَ ٱلْغَفُورُ ٱلرَّحِيمُ ﴿٥٣﴾ وَأَنِيبُوٓا۟ إِلَىٰ رَبِّكُمْ وَأَسْلِمُوا۟ لَهُۥ مِن قَبْلِ أَن يَأْتِيَكُمُ ٱلْعَذَابُ ثُمَّ لَا تُنصَرُونَ ﴿٥٤﴾ ﴾ الزمر: ٥٣ - ٥٤

"በላቸው «እናንተ በነፍሶቻችሁ ላይ ድንበር ያለፋችሁ ባሮቼ ሆይ! ከአላህ እዝነት ተስፋ አትቁረጡ፡፡ አላህ ኃጢኣቶችን በመላ ይምራልና፡፡ እነሆ እርሱ መሓሪው አዛኙ ነውና፡፡«ቅጣቱም ወደእናንተ ከመምጣቱና ከዚያም የማትርረዱ

[44] Al A'râf (The Ramparts), 7: 156.

ከመኾናችሁ በፊት ወደ ጌታችሁ (በመጸጸት) ተመለሱ። ለእርሱም ታዘዙ።" **(አዝዙመር፡ 53-54)**

የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ሰዎች መጥፎ ዕድልን በነገሮች ላይ እንዳያዋስዱ ከልክለዋል። ሁሉንም ነገሮች በበጎ እንድንመለከትና ለነገሮች መልካም ትርጓሜ እንድንሰጥ አዘውናል።[45]

ኢስላም ሰዎችን በክፉ መጠርጠርንና ስለ ሰዎች መጥፎ ማሰብን ከልክሎናል። ቅዱስ ቁርዓን እንደሚለው

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱجۡتَنِبُواْ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلظَّنِّ إِنَّ بَعۡضَ ٱلظَّنِّ إِثۡمٞۖ وَلَا تَجَسَّسُواْ وَلَا يَغۡتَب بَّعۡضُكُم بَعۡضًاۚ أَيُحِبُّ أَحَدُكُمۡ أَن يَأۡكُلَ لَحۡمَ أَخِيهِ مَيۡتٗا فَكَرِهۡتُمُوهُۚ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ تَوَّابٞ رَّحِيمٞ ١٢ ﴾ الحجرات: ١٢

እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ከጥርጣሬ ብዙውን ራቁ፤ ከጥርጣሬ ከፊሉ ኃጢአት ነውና። ነውርንም አትከታተሉ። ከፊላችሁም ከፊሉን አይማ። አንደኛችሁ የወንድሙን ስጋ የሞተ ኾኖ ሊበላው ይወዳልን? (መብላቱን) ጠላችሁትም፤ (ሐሜቱንም ጥሉት)። አላህንም ፍሩ። አላህ ጸጸትን ተቀባይ አዛኝ ነውና። **(አል ሁጅራት 49፡12)**

"ከሁሉም ፍጡር ጋር ለአላህ ሲሉ መኗኗር" የሚለው አስተሳሰብ የአማኞችን ልብ የገዛ ነው። አማኞች ለአላህ (ሱ.ወ) ካላቸው ፍቅር የተነሳ፤ ፍጡራንን በሙሉ በእዝነቱና ርህራሄ ይመለከታሉ። ሁሉም ፍጡራን ከአምላካቸው በአደራ እንደተሰጧቸው ያምናሉ። ከእርሱ የመጣን ማንኛውንም ነገር ደግሞ በደስታ ይቀበላሉ።

## ኢስላምና ማህበራዊ ወዳጅነት

በተፈጥሮዋቸው ሰዎች ማህበራዊ ናቸው። ሰው ብቻውን ሊኖር አይችልም። የሚጠጋው ወይም ወዳጅ እንዲሆነው የሚፈልገው ሰው ይፈልጋል። ከዚህም በላይ ሰው ሲፈጠር ደካማ ሆኖ ነውና ፍላጎቶቹን

---

[45] Bukhari, Tıb (Medicine), 19; Muslim, Selâm (Greeting), 102; Abu Dawud, Tıb (Medicine), 24/3919.

ሁሉ ማሟላት አይችልም፤ አጋዥ ያስፈልገዋል፡፡ ስለሆነም ሰዎች በማህበር እንደመኖራቸው እርስ በርስ መተጋገዝና መረዳዳት፤ ከአምላክ የተሰጣቸውን ኃላፊነት ተባብረው መወጣት አለባቸው፡፡ የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) "የአላህ እጅ (እርዳታ) ከማህበረሰብ ጋር ነው፡፡ ከማህበረሰቡ ያፈነገጠ በጀሀነብ መንገድ ላይ ያለ ነው" ሲሉ አስጠንቅቀዋል፡፡ (ቲርሚዚ፣ፊተን 7/267) በሌላ ንግግራቸውም "ማህበር እዝነት ነው፤ መለያየት ቅጣት ነው" ብለዋል፡፡ (አህመድ ኢብን ሐንበል 4፣278)

የኢስላም የአምልኮ ሥርዓት፣ ማህበራዊ ትዕዛዛት ይህን የሰዎች ማህበራዊነት የሚያጎለብቱ ናቸው - በጀምዓ መስገድ፣ ለጁመዓ መሰባሰብ፣ ሐጅ፣ ዘካ እንዲሁም በሰርግ፣ በሀዘን፣ ዝምድና መቀጠል፣ የታመመን መጠየቅ ወ.ዘ.ተ … ፡፡ እርግጥ ነው ሰው ለሰው ሲገናኝ አንዳንድ ተግዳሮቶች መኖራቸው አይቀርም፡፡ እነዚህን ተግዳሮቶች ለማለፍ ትዕግስትና ፅናት ወሳኝ ናቸው፡፡ ኢስላም በማህበር ለሚኖሩ እና የሰዎችን ችግር ለሚቀርፉ ሙስሊሞች ትልቅ ምልከታ አለው፡፡

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ከሰዎች ጋር በሙሉ መልካም ግንኙነት የነበራቸው ሲሆን እኩያን በጉርብጥ ምላሳቸውና ከይሲ ተግባራቸው ቢጎዷቸው እንኳ መልካም ፊት ከማሳየት አይቆጠቡም ነበር፡፡ አጎታቸው አባስ (ረ.ዐ) ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በሚደርስባቸው ጉዳት እጅግ ያዝን ነበር፡፡

"የአላህ መልዕክተኛ ሆይ! ሰዎች ሲያስቸግርዎ እመለከታለሁ፡፡ በሚበትኑብዎ አቧራ ሲረብሹዎ አይቻለሁ፡፡ ለምን ድንኳን አዘጋጅተው ከዚያው አይጠሩም?" አላቸው፡፡ ለዓለማት እዝነት የተላኩት ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲህ ብለው ነበር የመለሱለት "አይሆንም! አላህ እስካልወሰደኝ ድረስ ከነሱ መካከል እሆናለሁ፡፡ እግሬ ላይ ቢቆሙም፣ ልብሴንም ቢጎትቱ ወይም አቧራ ቢያለብሱብኝም ግድ የለኝም፡፡" (ዳርሚ፣ ሙቀዲማህ:14፣ኢብን ሸይባ፣ ሙሳነፍ7.90፣ኢብን ሰዒድ 193 ተመልከቱ)

ለተከታዮቻቸው ያዘዙትም ተመሳሳይ ነገር ነው። "ከሰዎች ጋር ተቀላቅሎ የሚያደርሱበትን መከራ የተቋቋመ ሙስሊም፣ መከራን በመሸሽ ለብቻው ከሚኖር ሙስሊም የተሻለ ነው" ብለዋል። (ቲርሚዚይ፣ቂያማ 55/2507)

ኢስላም ኑራችንን እንድናሸንፍ፣ ቤተሰብ እንድንመሠርት፣ ጊዜያችንን በአግባቡ እንድንጠቀም፣ የሰዎችን ችግር በመቅረፍ እንድንተጋ፣ ይህችን ምድር አኼራን ለማግኘት እንድንጠቀምባት፣ ሰዎችን ከጠማማ አስተሳሰብ አላቀን የእውነትን መንገድ እንድናሳይ፣ በዓለማዊው ኑሮዋችን ስኬታማ እንድንሆን ... ሲያዘን ፣ሕያው ህይወት እንድንኖር ስለሚፈልግ ነው። "የብናኝ ክብደት ያክልም መልካምን የሰራ ሰው ያገኘዋል፤ የብናኝን ክብደት ያክልም ክፉን የሰራ ሰው ያገኘዋል"[46]

قَالَ تَعَالَىٰ: أَعُوذُ بِاللَّهِ مِنَ الشَّيْطَانِ الرَّجِيمِ ﴿فَمَن يَعْمَلْ مِثْقَالَ ذَرَّةٍ خَيْرًا يَرَهُ ۝٧ وَمَن يَعْمَلْ مِثْقَالَ ذَرَّةٍ شَرًّا يَرَهُ ۝٨﴾ الزلزلة: ٧ - ٨

‹‹የብናኝ ክብደት ያክልም መልካምን የሠራ ሰው ያገኘዋል።›› ‹‹የብናኝ ክብደት ያክልም ክፉን የሠራ ሰው ያገኘዋል።›› **(አል-ዘልዘላ:- 7-8)**

ሲል ኢስላም ንቁ እና ተሳትፎ የሞላበት ሕይወት እንድንኖር እያበረታታን ነው።

[46] Az-Zalzala (The Earthquake), 99: 7-8; Al-An' am (Livestock), 6: 104; Az-Zumar (The Companies), 39: 41; Fussilat (Made Plain), 41: 46; Al-Jathiya (Kneeling), 45: 15.

## ኢስላም ለሰው ልጆች ትልቅ ዋጋ ይሰጣል

ኢስላም ከፍጥረታት ሁሉ ለሰው ልጆች ልዩ የሆነ ቦታ እና ክብር ይሰጣል፡፡ የቁርዓን ስለሰው እንዲህ አውስቷል፡-

﴿لَقَدْ خَلَقْنَا ٱلْإِنسَٰنَ فِىٓ أَحْسَنِ تَقْوِيمٍ ﴿٤﴾﴾ التين: ٤

‹‹ሰውን በጣም በአማረ አቋም ላይ ፈጠርነው፡፡›› **(አጥ-ጢን፡ 4)**

﴿وَلَقَدْ كَرَّمْنَا بَنِىٓ ءَادَمَ وَحَمَلْنَٰهُمْ فِى ٱلْبَرِّ وَٱلْبَحْرِ وَرَزَقْنَٰهُم مِّنَ ٱلطَّيِّبَٰتِ

وَفَضَّلْنَٰهُمْ عَلَىٰ كَثِيرٍ مِّمَّنْ خَلَقْنَا تَفْضِيلًا ﴿٧٠﴾﴾ الإسراء: ٧٠

‹‹የአደምንም ልጆች በእርግጥ (ከሌላው ፍጡር) አከበርናቸው፡፡ በየብስና በባህርም አሳፈርናቸው፡፡ ከመልካሞችም (ሲሳዮች) ሰጠናቸው፡፡ ከፈጠርናቸውም ፍጡሮች በብዙዎቹ ላይ ማብለጥን አበለጥናቸው፡፡››

**(አል ኢስራ 17፡70)**

አንድ ጊዜ ለቀስተኞች አሬሳ ተሸክመው ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በተቀመጡበት ፊት ያልፋሉ፡፡ የአላህ መልዕክተኛም (ሰ.ዐ.ወ) ተነስተው ይቆማሉ፡፡ አጠገባቸው የነበሩት ተከታዮቻቸው፡- ‹‹የአላህ መልዕክተኛ ሆይ! የአይሁድ ሬሳ ነው እኮ! " ይሏቸዋል፡፡ እርሳቸውም፡- "የሰው ልጆች አይደለንምን?" ሲሉ መለሱ፡፡ (ቡኻሪ፣ጀናይዝ፣50፤ ሙስሊም፤ጀናይዝ፣ 81)

ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) አላህ (ሱ.ወ) በታላቅ ጥንቃቄ ለፈጠረው ሰው ታላቅ ክብር ነበራቸው፡፡ በተጨማሪም ሰው መከበር ያለበት በህይወት ሲንቀሳቀስ ብቻ ሳይሆን ሞቶ ሬሳም ሆኖ ክብሩ ሊለየው እንደማይገባ አስገንዝበዋል፡፡

የዓላ ቢን ሙራ (ረ.ዐ) ገጠመኙን እንዲህ ያወሳል፡- "ከነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ጋር በብዙ ዘመቻዎች ላይ ተገኝቻለሁ፡፡ የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ሬሳ

ሲያገኙ ሙስሊምነቱንና ኢ አማኒነቱን ሳይጠይቁ ወዲያው እንዲቀበር ያዙ ነበር፡፡" ሐኪም፣526/1374)

እንግዲህ ሬሳ እንዲህ የተከበረው የሰው ልጅ ምን ያህል ዋጋ ቢኖረው ነው? አላህ (ሱ.ወ) እንዲህ ያስጠነቅቃል፡-

﴿ مِنْ أَجْلِ ذَٰلِكَ كَتَبْنَا عَلَىٰ بَنِي إِسْرَائِيلَ أَنَّهُ مَن قَتَلَ نَفْسًا بِغَيْرِ نَفْسٍ أَوْ فَسَادٍ فِي الْأَرْضِ فَكَأَنَّمَا قَتَلَ النَّاسَ جَمِيعًا وَمَنْ أَحْيَاهَا فَكَأَنَّمَا أَحْيَا النَّاسَ جَمِيعًا ۚ وَلَقَدْ جَاءَتْهُمْ رُسُلُنَا بِالْبَيِّنَاتِ ثُمَّ إِنَّ كَثِيرًا مِّنْهُم بَعْدَ ذَٰلِكَ فِي الْأَرْضِ لَمُسْرِفُونَ ﴿٣٢﴾ ﴾ المائدة: ٣٢

‹‹በዚህ ምክንያት በእስራኤል ልጆች ላይ እነሆ ያለ ነፍስ (መግደል) ወይም በምድር ላይ ያለማጥፋት (ካልሆነ በስተቀር) ነፍስን የገደለ ሰው ሰዎቹን ሁሉ እንደገደለ ነው፤ ሕያው ያደረጋትም ሰው ሰዎቹን ሁሉ ሕያው እንዳደረገ ነው ማለትን ጻፍን፡፡›› **(አል-ማዒዳ፡ 32)**

ራስንም ሆነ ሌላ ሰውን መግደል ፈፅሞ የተከለከለ ከመሆኑም በላይ፤ ይህንን የሚያደርጉት ከፍተኛ ቅጣት የሚጠብቃቸው ናቸው፡፡[47]

ታላቁ መውላና ጀላሉዲን አልሩሚ እንዲህ ይላል "የሰውን እውነተኛ ዋጋ ልገልፅ ብሞክር፤ ዓለም እኔም ባልበቃኝ ነበር፡፡ በሚያሳዝን አኳኋን የሰው ልጅ ለራሱ ያለውን ዋጋ አያቅም፤ አመለካከቱም ውራጅ ነው፡፡ ሰውን እጅግ ውድ ዋጋ እንዳለው ልብስ ብንመስለው፤ ለራሱ የሰጠው ዋጋ ግን እንደ መጣፊያ ጨርቅ ነው፡፡" (መጥናዊ VIII፣ አንቀፅ 1000-1001)

ኢስላም ሰው ከክብሩ ጋር የሚመጣጠን መብት ያስፈልገዋል የሚል አመለካከት አለው፡፡[48] ሰው ብቻ ሆኖ በመፈጠሩ መሠረታዊ የሠብዓዊ መብት የሚገባው ነው፡፡ የኢስላም ህግ ዓሊሞች ሰው ሆኖ መገኘት የሰብዓዊ መብት አስኳል ነው የሚል አቋም አላቸው፡፡ በመሆኑም

---

47 Bukhari, Diyât, 21; Tıbb (Medicine), 56; Muslim, ⵉmân,175..

48 For details on this subject see Kadir Mısıroğlu, *Islâm Dünya Görüşü (Islamic World View),* Istanbul 2008, pp.200-201; Prof. Dr. Recep Şentürk, *İnsan Hakları ve İslâm (Human Rights and Islam)*, Istanbul 2007

ሰብዓዊ መብቶችን በተመለከተ ያላቸው እይታ በኃይማኖት፣ ዘር፣ጾታ፣ መደብና ብሄር ያልተሸበበ ሁሉን አቀፍ እይታ የያዘ ነው። ይህ በቲዎሪ ደረጃ የሚያምኑበት ብቻ ሳይሆን ይተገብሩትም ነበር።[49]

[49] Prof. Dr. Recep Şentürk, Insan Hakları ve Islâm (Human Rights and Islam), pp. 13, 21.

# ምዕራፍ ሁለት

# የእምነት ማዕዘናት

## የአምልኮ ተግባራትና የአለማዊ ክንውኖች

በኢስላም፣ እምነት የሚቆመው (መሠረቱ የሚጣለው) በወህይ ላይ ነው። የሰው ልጆች ኃሳብ ሆነ ለነገሮች ያላቸው አረዳድ እዚህ ላይ ቦታ የላቸውም። የዕምነቱ መሠረቶች (አስኳል) በቅዱስ ቁርአን አሊያም በነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ንግግር (ሐዲስ) ውስጥ የሚገኙ ናቸው። እነዚህን መሠረቶች በሚከተለው መልኩ ጠቅለል አድርጎ ማቅረብ ይቻላል።

### ሀ. በአላህ ማመን

አላህ አለ። መጀመሪያም ሆነ መጨረሻም የለውም፤ ፍጡራኑንም ሆነ ማንንም ምኑንም የማይመስል ብቸኛና አንድ ነው። እርሱ ሕያው ነው፤ ለዚህም ከማንም ምንም አይነት እርዳታ አይፈልግም። በራሱ የተብቃቃ ነው።

አልተወለደም፣ አይወለድም። አባትም ሆነ ልጅ አይሆንም። በጊዜም ሆነ ቦታ አይወሰንም። ያለተጨማሪ አጋዥ ሁሉን ተመልካች፣ ሁሉን አዳማጭ፣ ሁሉን አዋቂ ነው።

በምድር ላይ፣ በውስጧም ሆነ በአካባቢዋ ላይ የምትካሄደዋን ቅንጣት እንቅስቃሴ ሳይቀር ያውቃል ከወደ ሰማያት ቀበሌ ሚደረጉ ምጥቀቶች፣ በምድርም ክበብ ውስጥም የሚደረጉ እንቅስቃሴዎች ከርሱ እውቀት ውጪ አይደሉም። ኢ አማኒያን የመጨረሻ ቀን

መምጣቱን ቢጠራጠሩም እውነታው ግን ከኃሳባቸው ፈፅሞ ተቃራኒ ነው፡፡

﴿ يَعۡلَمُ مَا يَلِجُ فِي ٱلۡأَرۡضِ وَمَا يَخۡرُجُ مِنۡهَا وَمَا يَنزِلُ مِنَ ٱلسَّمَآءِ وَمَا يَعۡرُجُ فِيهَاۚ وَهُوَ ٱلرَّحِيمُ ٱلۡغَفُورُ ۝٢ ﴾ سبأ: ٢

‹‹በምድር ውስጥ የሚገባውን ሁሉ ከእርሷም የሚወጣውን ከሰማይም የሚወርደውን በእርሷም ውስጥ የሚያርገውን ሁሉ ያውቃል፡፡ እርሱም አዛኙ መሓሪው ነው፡፡›› **(ሰብዕ፡ 2)**

አላህ በሴቶች ማህፀን ግድግዳ ላይ የተጣበቀችዋን ሽል ህያው ሆና ወደ ምድር ከምትመጣበት ቅፅበት ጭምር ያውቃል፡፡ ለሁሉ ነገሮች ያለው ዕውቀት እኩል ነው፡፡ ኃሳባችንን ከድብቁ የአእምሮዋችን ጓዳ ውስጥ ብንወሽቃት፤ ውጥናችንን ብንመሰጥረው ሆነ በወረቀት ብናሰፍረው ለርሱ ምንም ለውጥ የለውም፤ ሁሉንም ያውቃል፡፡ በርግጥ እርሱ ሁሉን የሚያውቅ ጌታ ነው፡፡ (አርረዕድ 13፡8-10፣ጣሃ 20፡7፣ አል ቀሰሶ 28፡69፣ አስ ሰጀዳ 32፡6፣ሁድ 11፡5)

ከእውቀቱ ሌላ አላህ (ሱ.ወ)ሁሉን ቻይና ፍጹም ኃያል ጌታ ነው፡፡ እርሱ እንዲህ ባይሆን ኖሮ ፍጡራኑንም ለማየት ባልታደልን ነበር፡፡ አላህ (ሱ.ወ) ስለ ራሱ ሲያስተዋውቅ እንዲ ይላል፡-

﴿ بَدِيعُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِۖ وَإِذَا قَضَىٰٓ أَمۡرٗا فَإِنَّمَا يَقُولُ لَهُۥ كُن فَيَكُونُ ۝١١٧ ﴾ البقرة: ١١٧

‹‹ሰማያትንና ምድርን ያለብጤ ፈጣሪ ነው፤ ነገርንም (ማስገኘት) በሻ ጊዜ ለርሱ የሚለው፡- «ኹን ነው፤» ወዲያውም ይኾናል፡፡›› **(አል በቀራ፡ 117)**

﴿ مَّا خَلۡقُكُمۡ وَلَا بَعۡثُكُمۡ إِلَّا كَنَفۡسٖ وَٰحِدَةٍۚ إِنَّ ٱللَّهَ سَمِيعُۢ بَصِيرٌ ۝٢٨ ﴾ لقمان: ٢٨

‹‹እናንተን መፍጠርና እናንተን መቀስቀስ እንደ አንዲት ነፍስ እንጂ ሌላ አይደለም፡፡ አላህ ሰሚ ተመልካች ነውና፡፡›› (**ሉቅማን፡ 28**)

﴿ وَلِلَّهِ غَيْبُ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضِ ۚ وَمَآ أَمْرُ ٱلسَّاعَةِ إِلَّا كَلَمْحِ ٱلْبَصَرِ أَوْ هُوَ أَقْرَبُ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَىْءٍ قَدِيرٌ ﴿٧٧﴾ ﴾ النحل: ٧٧

‹‹በሰማያትና በምድርም ያለው ሩቅ ምስጢር የአላህ ነው፡፡ የሰዓቲቱም ነገር (መምጣቷ) እንደዓይን ቅጽበት እንጂ አይደለም፡፡ ወይ እርሱ ይበልጥ የቀረበ ነው፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነው፡፡›› (**ነህል፡ 77**)

አላህ (ሱ.ወ) ፍጹም ፍቃድ ያለው ዘላለማዊ ነው፡፡ ያሻውን ነው የሚሰራው፡፡ የሚናገር ቢሆንም ድምፅም ሆነ ፊደላት አያሹትም፡፡ ከሰዎች ጋር በነቢያቱ አማካኝነት መፅሐፍቱን ልኮ ይገናኛል፡፡

ዩኒቨርሱንና በውስጡ ያሉትን፣ የሚታዩትንና የማይታዩትን የፈጠረው፤ ህያው አድርጎ የሚያቆየው፣ ጊዜያቸው ሲደርስ የሚገድላቸው፤ ቀናም ስትደርስ የሚቀሰቅሳቸው፤ በእርሱ ትዕዛዝ ላደሩ ምንዳ የሚሸልማቸው፤ ለአመፀኞች ውርደትን የሚያከናንባቸው አላህ ብቻ ነው፡፡ ይህንንም የሚያደርገው ያለአንዳች ረዳት ነው፡፡

አላህ (ሱ.ወ) ከየትኛው ዓይነት ጉድለትና ተመሳስሎሽ የጠሩ ፍፁም ባህሪያት አሉት፡፡[50]

## ለ. በመልዓክት ማመን

መልዓክት ከሰዎች በፊት ከብርሃን የተፈጠሩ ድንቅ ፍጡራን ናቸው፡፡ ፆታ የሌላቸው፤አላህን ብቻ የሚገዙ ናቸው፡፡ በርሱ ላይ ለማመፅ

[50] Prof. Dr. Bekir Topaloğlu, Article: Allah, *Diyanet Islâm Ansiklopedisi - Encyclopedia of Islam (Republic of Turkey, Presidency of Religous Affairs),* II, pp.488-489; Nesefî, *Akâid,* pp. 31-36.

የማይችሉ፣ ትዕዛዙን በፍፁም ጥራት የሚፈፅሙ ናቸው፡፡ አይተኙም፣ አይበሉም፣ አይጠጡም፣ አይደክማቸውም ወይም አይሰላቹም፤ ኃጢያትም አይነካቸውም፡፡ በአላህ ፍቃድና ትዕዛዝ የተለያዩ ገፅታዎችን ሊይዙ ይችላሉ፡፡ የተደበቀ ምስጢር አያውቁም፤ እውቀታቸው አላህ እስካሳወቃቸው መጠን ነው፡፡[51]

## መ. ለነብያት በተሰጡ መጽሐፍት ማመን

አላህ (ሱ.ወ) ሰዎች ይመሩበት፤ የእምነት አስተሳሰባቸውን ይነቅሱበት፣ አምልኮ ስርአታቸውን ይወስዱበት፣ ሥነምግባራቸውን ያረቅቁበትና ያመጥቁበት ዘንድ እና ሕይወታቸውን በአጠቃላይ ይቃኙበት ዘንድ ለነብያቱ የሰጣቸው መጽሐፍት አሉ፡፡ አስሱሁፍ አልዑላ ለተከበረው ኢብራሂም፣ ተውራት ለሙሴ፣ ዘቡር ለዳዊት፣ ኢንጂል ለእየሱስ፣ በመጨረሻም ቁርአን ለሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የተሰጡ መለኮታዊ መፅሐፍት ናቸው፡፡[52]

## ሠ. በነብያትና መልዕክተኞች ማመን

አደም የመጀመሪያው ነብይ ሲሆኑ ነብዩ ሙሐመድ የመጨረሻው ነብይ ናቸው፡፡ የአላህ ሰላምና እዝነት በሁሉም ላይ ይሁን፡፡ በነዚህ ሁለት ነብያት መካከል እጅግ ብዙ ነብያት ተልከዋል፡፡ ከነዚህ ውስጥ በስም የተጠቀሱ እንዳሉ ሁሉ በስም ያልተጠቀሱም አሉ፡፡ በነርሱ ላይ ባለን እምነት በመካከላቸው ምንም ዓይነት ልዩነት አናደርግም፡፡ ሁሉንም ያለምንም ቅድመ ሁኔታ እንቀበላለን፡፡ ሁሉም

---

51 Al-Baqara (The Cow), 2: 30-34; Al-A‘raf (Ramparts), 7:11, 27; Hûd, 11: 69-70; Al-Hijr, 15: 28, 51-52; Al-Isrâ (The Night Journey), 17: 61, 92; Al-Kahf (The Cave), 18: 50; Tâ Hâ, 20: 116; Sâd, 38: 71, 73; An-Najm (The Star), 53:5; At-Tahrîm (The Prohibition), 66: 6; At-Takwîr (The Compacting), 81: 20.

52 Al-Baqara (The Cow), 2: 85; Ȃli Imrân (The Family of Imran), 3: 3-4; An-Nisâ (Women), 4: 163; Tâ Hâ, 20: 133; An-Najm (The Star), 53: 36-37; Al-Hadîd (Iron), 57: 26-27; Al-A‘lâ (The Most High), 87: 18-19.

ነብያት ፍፁም ታማኝ፣ ቀናኢ፣ አዋቂ ኢስላምን ለሰዎች ለማድረስ ምንም ነገር ሳይቆጥቡ የሰሩ፣ ከኃጢያት የተጠበቁ ናቸው፡፡ የተለያዩ ተዓምራት ቢያሳዩም መለኮታዊ አልነበሩም፡፡

## ረ. በመጪው ዓለም ማመን

የዚህች ምድር ጉዞ የሚያበቃበት፣ የመጪው ዓለም የሚከፈትበት ዕለት በእርግጥ ይመጣል፡፡

ያመኑ፣ ነገር ግን የኃጢያት መዝገባቸው ድልብ የሆነባቸው ወይ ወደ ገሀነብ ገብተው ተቀጥተው ገነት ይገባሉ፤ አሊያም በጌታቸው ምህረት በቀጥታ ወደ ገነት ይገባሉ፡፡

## ሰ. በዕጣ ፈንታ ማመን

አላህ (ሱ.ወ) በባሪያዎቹ እስካሁን የተሰሩትን፣ ወደፊትም ሚሰሩትን ዙሪያ ገባ ስራዎች በሚሰሩበት ትክክለኛ ጊዜያቸውና ቦታቸው የሚያውቅ ነው፡፡ የተሰጠንን የምርጫ ፍቃድ ተጠቅመን የምናከናውናት የትኛውም አይነት ሥራ አላህ በሚያውቀው ቅፅበት ትፈፀማለች፡፡ ይህ ፈጣሪ በሰዎች ላይ የሚፈፅመው እጅ ጥምዘዛ ሳይሆን አዋቂነቱ የሚያስገድደው ዕውነት ነው፡፡ በግዛቱ ውስጥ የተፈፀመውን፣ እየሆነ ያለውን፣ እንዲሰራ እቅድ የተያዘለትን የማያውቅ አምላክ፣ ከደካማነት ውጭ ሌላ መለያ ሊኖረው አይችልም፡፡

ሰዎች ነፃ ፈቃድ ስለተሰጣቸው ያሻቸው መወሰንና ማድረግ ይችላሉ፡፡ ሆኖም ግን በምርጫችን የምንሰራትን እያንዳንዷን ነገር አላህ (ሱ.ወ) ያውቃታል፡፡ የሚያውቀውን ደግሞ ጽፎታል፡፡ አሁን አሁን ግርዶሽ መቼ እንደሚከሰት በሰኮንዶች የጊዜ ልኬት እንኳን ማስላት ይቻላል፡፡ ሳይንቲስቶች በሚያደርጉት ጥናትና ስሌት መሠረት የፀሐዩ ግርዶሽ

ከመከሰቱ በፊት ያውቃሉ፡፡ ይህን የአካላዊውን ዓለም እንቅስቃሴ ሰዎች አስቀድመው የሚያውቁበትም ሆነ ያወቁበት አጋጣሚ አለ፡፡

ሰዎች ምርጫ ስላላቸው ብዙ አማራጮችን መከተል ይችላሉ፡፡ አላህ (ሱ.ወ) የፈጠረው እነዚህን ምርጫዎች ነው፡፡ የነዚህ ምርጫዎች መፈጠር ዓላማ ደግሞ ለፈተና ነው፡፡ አላህ (ሱ.ወ) መልካም ነገሮችን ሲወድ፣ በመጥፎ ምርጫዎችና ድርጊቶች ይቆጣል፡፡[53]

## የአምልኮ አይነቶች ያዘሉት ጥበብ

እስካሁን ድረስ፣ በአጭሩ፣ የአላህን መኖር፣ ባህሪያቱን፣ ሰዎችን እንዴት ምርጥ አድርጎ እንደፈጠረ፣ በፍጥረት ዓለሙ ውስጥ ያላቸውን ልዩ ቦታ እና የተሰጣቸውን 3 ምርጥ ምቹ ሁኔታዎችና ችሮታዎች ለመመልከት ሞክረናል፡፡ እንግዲህ ይህ ሁሉ ስጦታ የተሰጠው ፍጡር በዚህች ምድር ላይ ሲኖር ምንም ኃላፊነት የለውም፤ ተጠያቂነትም የለበትም ማለት እንችላለን? እውቀትና ብልሀት እንዲሁም የምርጫ ፍቃድ የተሰጠው ሰው ይህ ሁሉ ስጦታ ካልተሰጣቸው እንስሶች ጋር እኩል ኃላፊነትና ተጠያቂነት አለበት ማለት ከሞራል አንፃር ያስኬዳልን? እንዴት ይህ ታላቅ የሆነ ፍጡር በመብላት፣ መጠጣት ማግባትና መውለድ፣ ከዚያም በሞት ዑደት ብቻ መወሰኑ ተገቢ ነው ብለን ልናስብ እንችላለን?

አላህ (ሱ.ወ) እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَمَا خَلَقْتُ ٱلْجِنَّ وَٱلْإِنسَ إِلَّا لِيَعْبُدُونِ ﴿٥٦﴾ ﴾ الذاريات: ٥٦

‹‹ጋኔንንና ሰውንም ሊግገዙኝ እንጅ ለሌላ አልፈጠርኳቸውም፡፡››
**(አዝ-ዛሪያት፡ 56)**

---

53 For details in the matter of creed see http://www.islamicpublishings.net/images/book/ingilizce/islamimanibadet_ing.pdf

﴿ وَٱعۡبُدۡ رَبَّكَ حَتَّىٰ يَأۡتِيَكَ ٱلۡيَقِينُ ٩٩ ﴾ الحجر: ٩٩

‹‹እውነቱም (ሞት) እስኪመጣህ ድረስ ጌታህን ተገዛ፡፡›› **(አል ሂጅር፡ 99)**

አምልኮ የባሪያነት፣ ትዕዛዝ አክባሪነትና እጅ ሰጪነት መገለጫ ነው፡፡ በሰፊ ትርጉሙ ሰው እንደ አምላኩ ፍቃድ ለመኖር የሚያደርገው የትኛውም አይነት እንቅስቃሴ ለምሳሌ፡- መብላት፣ መጠጣት፣ መተኛት፣ መነሳት፣ መናገር፣ ማፍቀር፣ ማሰብ ... ወዘተ ነው፡፡ አምልኮ አላህ (ሱ.ወ) ለባሪያው ለሰጠው ስጦታ ምስጋና ማቅረቢያ ነው፡፡

አምልኮ አምላኪውን ይጠቅማል፡፡ አምልኮ ሰዎች በዚህች ምድርና ሕይወት ግብስብስ እንዳይዋጡ፣ በቁስ አለም ወከባ እንዳይጨነቁ የሚጠብቃቸው፣ ራሳቸውን ወደ ላዕላይ አላማ ከፍ እንዲያደርጉ የሚያግዛቸው ነው፡፡ አምልኮ የሰውን ምንነት ይለጥጣል፡፡

የአምልኮ ጥቅም ከመጪው አለም ጋር ብቻ የተሳሰረ አይደለም፡፡ ከመንፈሳዊ ጥቅሞች ባሻገር አካላዊ ጥቅሞችም አሉት፡፡ ይህ ደግሞ የሚጠበቅ ነው፡፡ ምክንያቱም ኢስላም የሰዎችን ሁለንተናዊ የህይወት ጉዳዮች የሚያስተናግድ፣ መንፈሳዊም ሆነ አካላዊ ፍላጎቶች በእኩልነት ሚያሟላ ነው፡፡ የአምላክን ትዕዛዛት ለመፈፀም ሲባል የሚተገበሩ አምልኮዎች ምንዳዎችን እንደሚያስገኙ ሁሉ፤ ቁሳዊና አካላዊ ጥቅሞችም ይሰጣሉ፡፡እነዚህ ጥቅሞች አንዳንዶች ለሰዎች ግልፅ እንደመሆናቸው የተቀሩት ደግሞ ድብቅ ሊሆኑ ይችላሉ፡፡ ያም ሆነ ይህ ግን አምልኮ የመፈፀማችን ዋናው አላማ ለአላህ (ሱ.ወ) ያለንን ፍፁም ታዛዥነት ለማሳየት ነው፡፡ ለማነቃቂያ ስንል አምልኮዎች የሚያስገኙልንን ዓለማዊ ጥቅሞች እንደሚከተለው እናስቀምጣቸዋለን፡፡

**ሶላት:** ሶላት አንድ የአምልኮ ተግባር ሲሆን "አላህ አክበር" በመባል ተጀምሮ "አሰላምዓለይኩም ..." ተብሎ ይደመደማል፡፡ በውስጡ የሚነበነቡ ቃላትና በአካል የሚፈጸሙ እንቅስቃሴዎችን ይዟል፡፡[54] አላህ (ሱ.ወ) ሶላት ከመስገዳችን፣ ካዕባን ከመዞራችንም ሆነ ቁርአን መቅራት ከመጀመራችን በፊት ውዱዕ እንድናደርግ፤ አካላችንን፣ ልብሳችንን፣ አካባቢያችንን እንድናፀዳ አዟል፡፡ ውዱእንና ጉሰልን (ኃይማኖታዊ የገላ እጥበት) ጠለቅ ብለን ስንመረምርም፣ ኢስላም ለመንፈሳዊ ፅዳት ብቻ ሳይሆን ለአካላዊ ፅዳትም የሰጠውን ቦታ እንመለከታለን፡፡ በዚህ ምክንያት ሁሉም ኢስላማዊ የፍቅህ መፅሐፍት በዚህ ርዕስ ጉዳይ ነው የሚጀምሩት፡፡ ስለሆነም ከሶላት ጥቅሞች መካከል አንዱ የግለሰቦችንም ሆነ አካባቢ ፅዳት ማስጠበቅ መቻሉ ነው፡፡ ፅዳት በህይወት ውስጥ ያለው ቦታ ደግሞ ዝርዝር መግለጫ የሚያስፈልገው አይደለም፡፡

ከዚህ በተጨማሪ ሶላት ሰዎችን ከመጥፎ ነገር ይከለክላል፡፡ በስሜት ከመነሳሳትና በግድ የለሽ ህይወት ወዲህ ወዲያ ከመናወዝ ይጠብቃል፡ በቀን አምስት ጊዜ መስገዱ ሰዎች አምላካቸውን ከማስታወስ እንዳይዘናጉ አይነተኛ መድኃኒት ይሆናል፡፡ ስትንና ልጓም አልባ ፍላጎትን ሸብቦ ሰዎች ወደ ፅድቅ ጎዳና ዘወትር ያመላክታል፡፡ አንድ አማኝ ሶላቱን የአላህን ውዴታ ለማግኘት ብሎ ቢሰግድም ይህቿን አለም ስሜቱ ከሚወልዳቸው ከይሲ ተግባራት ጥፋት ይጠብቃታል፡፡[55]

---

[54] አንዳንድ ሰዎችሙስሊሞች ወደ ካዕባ ዞረው የሚሰግዱት፣ ካዕባውን እያመለኩ ስለሆነ ነው ብለው ያስባሉ፡፡ ይህ ትልቅ ስህተት ነው፡፡ ሙስሊሞች ካዕባን ሆነ ጠጥቁሩን ድንጋይ (አጀረል አስዋድን) አያመልኩም፡፡ በሶላት ወቅትም ወደነሱ መዞር ግድ አይደለም፡፡ ሙስሊሞች በሶላት ሲቆሙ ወደ ካዕባ ሕንፃ ሳይሆን የሚቆሙት ወደ ቦታው ነው፡፡ ካዕባው ቢፈርስ ወይም ቢጠፋ የሶላቱ አቅጣጫ አይለወጥም፡፡ የካዕባው ሕንፃ (መስጊድ) ኖረም አልኖረም፣ በሶላቱ አቅጣጫ ላይ የሚያመጣው ለውጥ የለም፡፡ (Prof. Dr. M. Hamidullah, *Islâm'aGiriş* (ኢስላምን መተዋወቅ ገጽ 108)

[55] Al-Ankabût (The Spider), 29: 45.

በቀን አምስት ጊዜ መስገድ ሰዎች ከዕለት ተዕለት አሰልቺ የህይወት ትንቅንቅ እፎይታ ይሰጣቸዋል፡፡ ከቁሳዊው ዓለም ጭንቅ መንጭቆ በማውጣት ከአላህ (ሱ.ወ) ጋር እንዲገናኙ፣ ለእለታዊ ምስጋና እድል እንዲያገኙ፣ታዛዥ ባርያነታቸውንም እንዲያረጋግጡ ያስችላቸዋል፡፡ ሶላት የዚህች ዓለም ብቸኛ ተቆጣጣሪ፣ አስተናባሪ እና አንቀሳቃሽ አላህ (ሱ.ወ) ብቻ እንደሆነ እንድናስታውስ ያደርገናል፡፡ በሶላት ውስጥ፣ በተለይ በሱጁድ ወቅት ከዚህ ሁሉን ቻይና ሰላምና እፎይታ ሰጪ አምላክ ጋር ይበልጥ እንድንቀራረብ ስለሚያደርገን፣ ፍፁም ወደ ሆነ የደስታ  እና ፅኑ ዓለም ያሸጋግረናል፡፡ አሜሪካዊው ሰለምቴ ማት ሴልስማን (Matt Salesman) ፣ ሚሲዮናዊ ነበር፣ እንዲህ ነበር ያለው "ስሰግድ፣ በተለይ የጁሙዓ ሶላትን፤ ፊፅሞ መረጋጋት እና እርካታ ይሰማኛል፡፡ ነፍሴ በርግጥ ሰኪና የምታገኝባቸው ልዩ ጊዜያት በመስጊድ የማሳልፋቸው ጊዜያት ናቸው፡፡"[56]

የቶሮንቶ ዩንቨርሲቲው ሰለምቴ ቲሞቲ ጊያኖቲም (Timothy Gianotti) ሲናገር "ሱጁድ ሳደርግ ሰላምን እንደጨበጥኳት፤ ፍፁም ደህንነት ባለበት የሰላም ምድር ላይ እንዳለሁ ይሰማኛል፡፡ ሱጁድ ሳደርግ የሚሰማኝ ስሜት ከሩቅ አገር ተመልሼ ወደ ቤቴ እንደገባሁ አይነት ነው፡፡ ወደ አላህም እንደደረስኩ ይሰማኛል፡፡ ለመግለፅ የምችለው እንደዚሁ ነው፡፡ ሶላት የሰላምና ሰኪና ምንጭ ነው፡፡"[57]

ሶላት የመንፈሳዊ ሕያውነት ምንጭ እንደሆነ ሁሉ አካላዊ ፈውስም ሰጪ ነው፡፡ ሶላት የተለያዩ የሰውነቶቻችንን ጡንቻዎች እንዲንቀሳቀሱ፣ አጥንቶቻችን እንዲተጣጠፉ ስለሚያደርግ አካላዊ እንቅስቃሴን ይፈጥራል፡፡ የሙስሊሞች ሕይወት ማዕከላዊነት እንዲኖረው ያደርጋል፡፡ ሶላት በተወሰኑ ጊዜያት እና በተወሰነ የህግ

---

56 Ahmet B◌ken - Ayhan Eryiğit, *Yeni Hayatlar (New Lives),* I, 49.

57 Ahmet Boken - Ayhan Eryiğit, *Yeni Hayatlar (New Lives),* I, 19.

ማዕቀፍ ውስጥ ስለሚካሄድ፣ የሰጋጅ ህይወት ሥርዓት ያለውና የተረጋጋ እንዲሆን ያስችላል፡፡

ምንም እንኳን ሰዎች በተናጠል ሶላት መስገድ ባይከለከሉም፣ ኢስላም ተሰብስበው እንዲሰግዱ አጥብቆ ያዛል፣ ያበረታታል፣ ይፈልጋል፡፡ ምክንያቱም ሶላትን በህብረት መስገድ የሰዎች እኩልነት በልባችን እንዲሰርፅ ያደርጋል፡፡ ሰዎች የዘር፣ የቀለም፣ የቋንቋ ፣ የስልጣንም ሆነ ክብር ልዩነት ሳይለያቸው በእውነተኛ እኩልነት ሊሰባሰቡበት የሚችሉበት አጋጣሚ ካለ ሶላት ዋነኛው ነው፡፡ የዑማነት ንቃተ ህሊና እና ስሜት እንዲዳብር ያደርጋል፡፡ የጋራ ጉዳዮች (አጀንዳዎች) እንዲዳብሩ ያስችላል፡፡ የጋራ ጉዳዮችን በዳበሩበትና የጋራ ዓላማ በጠራበት ማህበረሰብ ውስጥ የግለሰቦችና ጥቃቅን ልዩነቶች በቀላሉ ሊፈቱ፣ የወንድማማችነትና እኩልነት ስሜት በልባችን ውስጥ እንዲያብብ፣ ኃይማኖታዊ ስሜት እንዲጎመራ መንገዱን ያመቻቻል፡፡

በርግጥ ሶላትን በቀን አምስት ጊዜ መስገድ በጣም ቀላል ነገር ነው፡፡ በ24 ሰዓታት ውስጥ የሚወስዱት ጊዜ ድምር 24 ደቂቃዎችን ብቻ ነው፡፡ ሆኖም ግን በነዚህ 24 ደቂቃዎች የሰው ልጅ እጅግ ብዙ ጥቅሞች ያገኛል፡፡

***ፆም፡*** ጎህ ከመቅደዱ አንስቶ እስከ ፀሐይ መጥለቂያ ጊዜ ከምግብ፣ ከመጠጥ እና ከግብረስጋ ግንኙነት መታቀብ ማለት ነው፡፡ ይህ በዓመት ለአንድ ጊዜ በረመዳን ወር ለ29 ወይም 30 ቀናት የሚፈፀም አምልኮ ነው፡፡

የትዕግስትን፣ ራስን የመቆጣጠርና ስሜትን የማሸነፍ እሴቶች እንዲዳብሩ ስለሚያደርግ የሥነ ምግባር ይዞታችን እንዲነጥር ያደርጋል፡፡ ሰዎች ከመብላት፣ ከመጠጣት እና ወሲብ ስሜት ባሪያነት ጋሻ ሆኖ ስለሚታደጋቸው ክብራቸውን ይጠብቃል፡፡ጿሚዎች የቆራጥነት፣ የፅኑነት፣ የተብቃቂነት፣ የወሳኝነትና የታጋሽነት ውብ እሴቶችን እንዲጎናፀፉ ያደርጋል፡፡ የፈላጊነት ስሜት እንዲሰማን ስለሚያደርግ ለተሰጡን ስጦታዎች አመስጋኝም እንድንሆን ያስታውሰናል፡፡ ልባችንንም በፍቅርና እዝነት ይሞላል፡፡ ሰለሆነም ፃም የማህበረሰብ ጠር ከሆኑት ስግብግብነት፣ ቅናትና ምቀኝነት የሚታደግ ፍቱን መድኃኒት ነው፡፡ በመሆኑም ፃም በኛ ብቻ ሳይሆን ባለፉት ህዝቦች ላይ ግዴታ መሆኑ የሚደንቅ አይሆንም፡፡

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ كُتِبَ عَلَيۡكُمُ ٱلصِّيَامُ كَمَا كُتِبَ عَلَى ٱلَّذِينَ مِن قَبۡلِكُمۡ لَعَلَّكُمۡ تَتَّقُونَ ١٨٣ أَيَّامٗا مَّعۡدُودَٰتٖۚ فَمَن كَانَ مِنكُم مَّرِيضًا أَوۡ عَلَىٰ سَفَرٖ فَعِدَّةٞ مِّنۡ أَيَّامٍ أُخَرَۚ وَعَلَى ٱلَّذِينَ يُطِيقُونَهُۥ فِدۡيَةٞ طَعَامُ مِسۡكِينٖۖ فَمَن تَطَوَّعَ خَيۡرٗا فَهُوَ خَيۡرٞ لَّهُۥۚ وَأَن تَصُومُواْ خَيۡرٞ لَّكُمۡۖ إِن كُنتُمۡ تَعۡلَمُونَ ١٨٤ ﴾ البقرة: ١٨٣ - ١٨٤

‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ ጾም በነዚያ ከናንተ በፊት በነበሩት (ሕዝቦች) ላይ እንደ ተጻፈ በናንተም ላይ ተጻፈ (ተደነባ) ልትጠነቀቁ ይከጀላልና፡፡ የተቆጠሩን ቀኖች (ጹሙ)፡፡ ከእናንተም ውስጥ በሽተኛ ወይም በጉዞ ላይ የኾነ ሰው ከሌሎች ቀኖች ቁጥሮችን መጾም አለበት፡፡ በእነዚያም ጾምን በማይችሉት ላይ ቤዛ ድኻን ማብላት አለባቸው፡፡ (ቤዛን በመጨመር) መልካምንም ሥራ የፈቀደ ሰው እርሱ (ፈቅዶ መጨመሩ) ለርሱ በላጭ

ነው። መጾማችሁም ለናንተ የበለጠ ነው፤ የምታውቁ ብትኾኑ (ትመርጡታላችሁ)።›› **(አል በቀራ፡ 183-184")**

የፆም መንፈሳዊ ፋይዳ እንዲገኝ ከተፈለገ አንድ ሰው ከውሸት፣ ሐሜት፣ ማንጓጠጥ፣ ስድብ፣ ርግማን፣ ጥል እና ከሌሎች መሰል ኃጢያቶችና ፀያፍ ባህሪያት መራቅ አለበት። የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ጺሚ የሆነ ሰው ያልተገቡ ባህሪያት ቢፈፀሙበት በእርጋታ እንዲያሰልፉቸው (እንዲርቅ) መክረዋል። ፆም ሰዎች ጤነኛ እና የበለጠ አምራች እንዲሆኑ ያደርጋል። ይህን ከዛፎች ወቅታዊ ሕይወት አንፃር ማየት እንችላለን። ዛፎች በበጋ ወቅት ቅጠሎቻቸው በብዛት ይረግፋሉ፣ አንዳንዶች መለምለማቸውን ያቆማሉ። ሆኖም የዝናብ ወቅት ሲመጣና ዝናቡም ሲዘንብ፣ ከዚያም የፀደይ ወራት ሲገባ ቅጠሎቻቸው ይለመልማሉ፣ ፍሬዎችንም በገፍ ይሰጣሉ፣ ያመርታሉ። ለበለጠ ምርታማነት ዕረፍት የማይፈልግ ነገር ለም። ማሽኖች ከብዙ የስራ ጊዜያት በኋላ እንዲያርፉ ቢደረግ ብቃታቸው ይጨምራል።

የሕክምና ጥናቶች የፆምን ጠቃሚነት ብቻ ሳይሆን የጾም ጊዜያት ውስንነት ወሳኝ እንደሆኑ ያመለክታሉ። በጥናቶቹ መሰረት ከሰላሳ ቀናት በታች መጾም ከጾም የሚገኘውን ጥቅም በቂ እንደማያደርገው ሁሉ ከ40 ቀናት በላይ መፆም ፆምን ወደ ልምድነት እንዲለወጥ ከማድረጉም በላይ በነዚህ ቀናት ከመብላትና ከመጠጣት የሚገኘው ጥቅም እንዲታጣ ያደርጋል። ከቅርብ ጊዜ ወዲህ ለአንዳንድ ከፍተኛ ሕመሞች ፈውስነት የአጭር እና ረጅም ጊዜ ፆሞች እንደ ፍቱን አማራጭነት ቀርበዋል።[58] ፆም አእምሮአዊና መንፈሳዊ ሂደቶች ጤናማ እንዲሆኑ ያደርጋል።

[58] Prof. Dr. M. Hamîdullah, *Introduction to Islam (Islâm'a Giriş),* pg. 104.

የፆም ዓላማ አካልን ማሰቃየትና አላስፈላጊ ጫና ውስጥ መክተት አይደለም፡፡ የአላህን መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ለጾም መያዣ ሌሊት ተነስተን እንድንበላ (ሱሁር) እና ፀሐይ ከጠለቀች በኋላ ለ"ፍጡር" እንድንቻኮል አዘውናል፡፡[59]

የጾም ዓላማ ለአላህ (ሱ.ወ) ያለንን ታዛዥነት ለማሳያ፣ ስሜታችንን ማግሪያ፣ ተቅዋን (የአላህ ያለንን ፍራቻ) ማዳበሪያ እና አላህ (ሱ.ወ) የሚደሰትበትን ከባቢ መፍጠሪያ (የግለሰቦችንና ማህበረሰብን ሰናይ ይዞታ ማሻሻያ) ነው፡፡

**ዘካ፡** ኃብታቸው ከተወሰነ መጠን በላይ በሆኑ ባለኃብቶች ላይ እንዲከፍሉ ግዴታ የተደረገባቸው የድሆች ኃቅ ነው፡፡

﴿ إِنَّمَا ٱلصَّدَقَٰتُ لِلْفُقَرَآءِ وَٱلْمَسَٰكِينِ وَٱلْعَٰمِلِينَ عَلَيْهَا وَٱلْمُؤَلَّفَةِ قُلُوبُهُمْ وَفِى ٱلرِّقَابِ وَٱلْغَٰرِمِينَ وَفِى سَبِيلِ ٱللَّهِ وَٱبْنِ ٱلسَّبِيلِ ۖ فَرِيضَةً مِّنَ ٱللَّهِ ۗ وَٱللَّهُ عَلِيمٌ حَكِيمٌ ﴿٦٠﴾ ﴾ التوبة: ٦٠

‹‹ግዴታ ምጽዋቶች (የሚከፈሉት) ለድኾች፣ ለምስኪኖችም፣ በርሷም ላይ ለሚሠሩ ሠራተኞች፣ ልቦቻቸውም (በእስልምና) ለሚለማመዱት፣ ጫንቃዎችንም (በባርነት ተገዢዎችን) ነጻ በማውጣት፣ በባለ ዕዳዎችም፣ በአላህ መንገድም በሚሠሩ፣ በመንገደኛም ብቻ ነው፡፡ ከአላህ የተደነገገች ግዴታ ናት፡፡ አላህም ዐዋቂ ጥበበኛ ነው፡፡›› **(አልተማም 9:60)**

ዘካ ኃብታሞችን ኃብት ከሚፈጥረው የስግብግብነትና ምቀኝነት አጉል ባህሪ ስለሚጠብቃቸው፤ የድሆች ንብረት ከንብረታቸው ጋር እንደተቀላቀለ እንዲረዱ ስለሚያደርጋቸው በሰዎች መካከል የመተሳሰብ ስሜትና ወንድማማችነትን ስለሚፈጥር የህብረተሰቡን

---

59 Bukhari, Savm, 45; Muslim, Sıyâm, 48; Tirmizî, Savm,17/708.

ጤንነት ይጠብቃል፡፡ በኃብታምና ደኃ መካከል ያለውን ልዩነት ያጠባል፡፡ ዓለማችን የተለጠፈባትን አስቀያሚ የድህነት ጠባሳ ይገፋል፡

በኸሊፋው ዑመር ኢብንአብዱልዓዚዝ ጊዜ ዘካ በግዛታቸው የሚቀበል ጠፍቶ የዘካ ሀላፊዎቻቸውን ወደ አፍሪቃ ቢልኩም እንዲሁ የሚቀበል ስለጠፋ በገንዘቡ ብዙ ባሪያዎችን ነፃ አውጥቶናል፡፡[60]

ዘካ በተለያዩ የኢኮኖሚ ደረጃ ላይ ያሉትን ሕዝቦች የሚያቀራርብ በመሆኑ የማህበረሰብን አንድነት ይጠብቃል፡፡ በዚህም ምክንያት ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) "ዘካ የኢስላም ድልድይ ነው" ብለዋል፡፡[61]

ቀታዳ የተባለ ዓሊምም ሌላ የድልድይነቱን ገፅታ አሳይቷል፡፡ "ዘካ በገነትና ገሃነም መካከል የተዘረጋ ድልድይ ነው፡፡ ዘካን (በአግባቡ) የከፈለ ሁሉ ድልድዩን ተሻግሮ ገነት ገብቷል፡፡[62]

ዘካ ከተቀባይ ይልቅ ለሰጪው ልዩ ትርጉም አለው፡፡ ዘካ ማንፃት፣ ማጥራት፣ መጨመር፣ ማትረፍ የሚሉ ትርጉሞች ስላሉት እንደ ትርጉሙ ዘካ ሰጪውን ከመንፈሳዊ በሽታዎችና ክፋቶች ያነፃዋል፣ ያጠራዋል፤ ኃብቱንም ይጨምርለታል፡፡[63]

የሰዎችን ነፍስና ቀልብ ማጥራት፤ ግለሰቦችንና ማህበረሰብን መለወጥ ነብያት የተላኩበት መሠረታዊ አላማ ነው፡፡ ዘካ የሰዎችን ራስ ወዳድነትና ንብረት የመያዝ ፍላጎት ሥርዓት ያስይዛል፡፡ በተጨማሪም ዘካ ኃብታሞች ለተሰጣቸው ስጦታ አላህን የሚያመሰግኑበት ዕድል (አጋጣሚ) ይሰጣቸዋል፡፡ ሰዎች አመስጋኝ በሆኑ ቁጥር ኃብታቸው እንደ ሚጨምር፤ ነገር ግን በተሰጣቸው

---

60 See. Bûtî, *Fıkhu's-sîre,* Beirut 1980, p. 434.

61 Beyhakî, *Şuab,* III, 20, 195; Heysemî, III, 62.

62 Abdurrazzâk, *Musannef,* IV, 108.

63 At-Tawba (Repentance), 9: 103; Saba (Sheba), 34: 39.

ችሮታ የማያመሰግኑ ከሆነ ኪሳራው ከባድ እንደሆነ አላህ (ሱ.ወ) ይናገራል፡፡[64]

ዘካ የማይሰጥ ከሆነ እነዚህ ሁሉ ጥቅሞች የውሃ ሽታ ከመሆናቸውም በተጨማሪ በግለሰቦችና በማህበረሰቡ (ህብረተሰቡ) ላይ የሚደርሰው ጥፋት ከፍተኛ እንደሚሆን ግልፅ ነው፡፡ ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ዘካ እንደ ከባድ ሸክም መታየት በሚጀምርበት ወቅት፣ በሂደትም ሰዎችም መክፈል ማቆም በሚጀምሩበት ጊዜ፣ ጥፋቶች እየመጡ እንደሆነ አስጠንቅቀዋል፡፡[65] በአንድ ንግግራቸው እንዲህ ብለዋል፡-"ዘካ መክፈል የተወ ህዝብ ዝናብ ያጣል፤ እንስሳዎች ከጠፉ ደግሞ ዝናቡ ሙሉ ለሙሉ ይጠፋል" (ኢብን ማጃህ፣ፊተን፣ 22፤ሐኪም IV፣ 583/8623).

**ሐጅ:** ኃብቱና ጤንነቱ ያላቸው ሙስሊሞች ቢያንስ በሕይወት ዘመናቸው ለአንድ ጊዜ ወደ አላህ ቤት (ካዕባ፣መካ) የሚያደርጉት ጉዞ ነው፡፡ ሰዎች በሐጅ ወቅት ብዙ የአምልኮ ተግባራትን፣ ፀሎቶችን ስለሚያደርሱ አላህንም በእያንዳንዱ እርምጃ በማስታወስ የእርሱን ፍቅር በልቦቻቸው ውስጥ የሚያፀኑበት ነው፡፡ ትህትህና፤ በአምላካቸው ላይ ፍፁም መተማመን፣ ትዕግስት፣ ፍፁም ታዛዥነት፣ ቀናኢነት፣ የጊዜና ሥራ አክባሪነት፣ ለሞትና የመጨረሻው ቀን ዝግጁነት፣ የትኛውንም አይነት ፍጡር ከመጉዳት የመታቀብ ተጨማሪ ጥቅሞች የሚያገኙበት ነው፡፡ ሐጅ በተለያዩ ቦታዎች የተለያዩ ተግባሮች የሚፈፀምበት የአምልኮ ተግባር ስለሆነ በውስጡ የተለያዩ መንፈሳዊ ጥቅሞች ይዟል፡፡ እያንዳንዱ ግለሰብ ከተለያዩ የሀጅ ገፅታዎች የተለያዩ ጥቅም ያገኛል፡፡

---

[64] Ibrâhîm, 14: 7.
[65] Tirmizi, Fiten, 38/2210, 2211.

ሐጅ የሰውን ጠቅላላ ማንነት ወደ መንፈሳዊ ሕይወት ይለውጣል። ምክንያቱን የሐጅ አምልኮ በእዝነት፣ ርህራሄ እና ፍቅር የተሞላ በመሆኑ ነው። በዚህ የአምልኮ ወቅት ማደንም፣ ዝንብ መግደልም ሆነ አንድ ቅጠል ከቅርንጫፍ መገንጠል በአጠቃላይ የአላህን ፍጡር መጉዳት ክልክል ነው።

ሐጅ ለማድረግ ከየአገሩ የተሰባሰቡ ሙስሊሞች በተመሳሳይ ቦታና ጊዜ ፍፁም በሆነ መንፈሳዊ አንድነት ይተሳሰራሉ። አገር፣ ዘር፣ ቀለም፣ ልብስ የመሳሰሉት ፅንሰ ሀሳቦች ፈፅሞ ይጠፉና በኢስላማዊ ወንድማማችነት ይተካሉ። በዚህ ልዩ ወቅት የፋብሪካ አለቃ ከሠራተኛው፣ ሃብታሙ ከደሃው፣ ሊቁ ከመሃይሙ፣ መሪው ከተመሪው ጋር በአንድ ልብስ፣ በአንድ ቦታ፣ በአንድ መስመር እኩል ይሆናል። ሙስሊሞች የሌላውን ወንድሙን ችግርና መከራ ያዳምጣል፤ አይቶት ለማያውቀው አገር አይቷቸው ለማያውቃቸው ወንድምና እህቶች መልዕክት ያደርሳል።[66]

ከላይ በመጠኑም ቢሆን ለመጠቃቀስ በሞከርናቸው የአምልኮ አይነቶች ኢስላም የህይወት መንገድ እንደሆነ ለማየት ሞክረናል። ኢስላም በተወሰኑ ቀናት ወይም ሳምንታዊ አለያም ወራት የተቀጠቡ የአምልኮ ስርአት ስብስብ አይደለም። ኢስላም አንድ ሰው ከመወለዱ በፊት ጀምሮ እስከ እለተ ሞቱ ያለውን የጉዞውን ትክክለኛ አቅጣጫ የሚያመለክት ነው። ቲሞቲ ጊያኖቲ ሲናገር "ኢስላምን ስመርጥ፣ ይህ ኃይማኖት ምድርን በሙሉ ወደ አምልኮ ቦታ ለመለወጥ የመጣ እንደሆነ አውቄ ነበር። ጥቃቅን የህይወት ገፅታዎችን ጭምር ሚመለከት በመሆኑ የቤተ መቅደስ አስፈላጊነትንም ያከሸፈ ነው። ለምሳሌ ሶላት አንድ ሰው የትም ቦታ ቢሆን አላህን ሊያስታውስ

---

66 For details on worship see http://www.islamicpublishings.net/images/book/ingilizce/islamimanibadet_ing.pdf.

በሚችል መልኩ የቀረበ ቀላል ነገር ነው።" (Ahmet Boken Ayhan Eryigit, Yeni Hayatlar (New Lives), I 15-16)

## ኢስላማዊ እቀባዎች

አላህ (ሱ.ወ) ከመልካምና ንፁህ ነገሮች እንድንጠቀም ሲፈቅድልን፣ እንዳንጠቀማቸው እና እንዳናደርጋቸው የከለከለን ነገሮች አሉ። አላህ (ሰ.ወ) እንድንታቀባቸው የከለከለን ነገሮች ሥለሚጎዱን ብቻ ነው። አላህ (ሰ.ወ) እንዲህ ይላል፡-

﴿ قُلْ إِنَّمَا حَرَّمَ رَبِّيَ ٱلْفَوَٰحِشَ مَا ظَهَرَ مِنْهَا وَمَا بَطَنَ وَٱلْإِثْمَ وَٱلْبَغْيَ بِغَيْرِ ٱلْحَقِّ وَأَن تُشْرِكُوا۟ بِٱللَّهِ مَا لَمْ يُنَزِّلْ بِهِۦ سُلْطَٰنًا وَأَن تَقُولُوا۟ عَلَى ٱللَّهِ مَا لَا تَعْلَمُونَ ﴿٣٣﴾ ﴾ الأعراف: ٣٣

‹‹ጌታዬ እርም ያደረገው መጥፎ ሥራዎችን፣ ከርሷ የተገለጸውንና የተደበቀውን ኃጢኣትንም፣ ያላግባብ መበደልንም፣ በርሱም ማስረጃ ያላወረደበትን (ጣዖት) በአላህ ማጋራታችሁን፣ በአላህም ላይ የማታውቁትን መናገራችሁን ብቻ ነው» በላቸው።›› **(አል አእራፍ: 33)**

ኃጢያትና ወንጀሎች የሰዎችን መንፈሳዊ ይዞታ እና አካላዊ (ቁሳዊ) ሃብት የሚያወድሙ ናቸው። ሆኖም ግን ሰይጣንና ወዳቂ ስሜታችን እነዚህን ነገሮች ውብ አድርገው ያቀርቡልናል። በዚህ የተታለሉ ሰዎች መጨረሻቸው ጥፋትና ኪሳራ እንደሆነ በግልፅ ታይቷል።

እንድንጠቀምባቸው የተፈቀዱ ነገሮች ስፍር ቁጥር የላቸውም። ከዚህ በተቃራኒ የተከለከልናቸው ነገሮች እጅግ ጥቂቶች ናቸው። ሆኖም ግን የአዳም ልጅ ብዙ የተፈቀዱለት ነገሮችን ትቶ በጥቂት ክልክል ነገሮች ስር ሲልከሰከስ መታየቱ የሚገርም ነው።

## ወለድ (አራጣ)

ምንም ሥራ ሳይሰሩ ገንዘብ በማግኘት መሠረታዊ አስተሳሰብ ላይ የተመሠረተው ወለድ፣ ከውጪ ሲታይ ለሥግብግቦች መልካም መስሎ ቢታያቸውም እውነታው ግን ረዳት የሌላቸውን ከመበዝበዝ ውጪ ምንም ፋይዳ የለውም፡፡በአላህ ፍጡራን መብት ላይ የሚፈጸም ታላቅ ጥሰት ነው፡፡

የአገርን ኢኮኖሚ የሚቦረቡር ምስጥ፣ ኃይማኖታዊና የሞራል እሴቶችን የሚያንኳጥጥ ነገር ነው፡፡ ኃብታሞችን የበለጠ ኃብታም፣ የድሆችን ሥጋ በልቶ ደማቸውን መጥጦ በአጥንታቸው እንዲቀሩ የሚያደርግ በዝባዥ ሥርዓት ነው፡፡ ወለድ በመሰረቱ የጥፋት መልዕክተኛ በመሆኑ፣ በኢኮኖሚ ባለሙያዎች የምርጥ ኢኮኖሚ ባለቤትነት መገለጫ ሲናገሩ ግሽበትና ወለድ "አልባ" ነው ይላሉ፡፡

በተጨማሪም ወለድ ብዙ ቀውሶችን የሚያስከትል ቆሻሻ ነገር ነው፡፡ ሰው ሰራሽ የዋጋ ግሽበት ያመጣል፤ መተሳሰብን፣ መረዳዳትን፣ ፍቅርን፣ እዝነትን፣ እና ርህራሄን ጨፍጭፎ ራስ ወዳድነትና ለዑለ ራስነትን ያጋግማል፡፡ የትም ፍጪው ... አይነት አስተሳሰብ ያዳብራል፡፡

ወለድ ሰዎችን ከስራና አምራችነት ያሳንፋል፡፡ ከግብርናና ከንግድ አርቆ ገንዘብን በገንዘብ በመለወጥ በሽታ እንዲለከፉ ያደርጋል፡፡ ይህ ደግሞ ምርታማነትን ይቀንሳል፡፡

ገንዘብን በገንዘብ እየለወጡ ትርፍ ማግኘት (ወለድ)፣ ምንም እንኳን ወለድ በዪዎችን ለአሁኑ የጠቀማቸው ቢመስላቸውም፤ የጉልበትና ካፒታል (Labour- Capital) ግንኙነትን ቀልብሶ የሚበላ ነው፡፡ ቅዱስ

ቁርአን ወለድ በዬዎች በአላህና መልዕክተኛው (ሰ.ዐ.ወ) ላይ ጦርነት እንደከፈቱ ይናገራል፡፡[67]

﴿ ٱلَّذِينَ يَأْكُلُونَ ٱلرِّبَوٰا۟ لَا يَقُومُونَ إِلَّا كَمَا يَقُومُ ٱلَّذِى يَتَخَبَّطُهُ ٱلشَّيْطَٰنُ مِنَ ٱلْمَسِّ ۚ ذَٰلِكَ بِأَنَّهُمْ قَالُوٓا۟ إِنَّمَا ٱلْبَيْعُ مِثْلُ ٱلرِّبَوٰا۟ ۗ وَأَحَلَّ ٱللَّهُ ٱلْبَيْعَ وَحَرَّمَ ٱلرِّبَوٰا۟ ۚ فَمَن جَآءَهُۥ مَوْعِظَةٌ مِّن رَّبِّهِۦ فَٱنتَهَىٰ فَلَهُۥ مَا سَلَفَ وَأَمْرُهُۥٓ إِلَى ٱللَّهِ ۖ وَمَنْ عَادَ فَأُو۟لَٰٓئِكَ أَصْحَٰبُ ٱلنَّارِ ۖ هُمْ فِيهَا خَٰلِدُونَ ﴿٢٧٥﴾ ﴾ البقرة: ٢٧٥

‹‹እነዚያ አራጣን የሚበሉ ያ ሰይጣን ከመንካቱ የተነሳ የሚጥለው ሰው (ከአውድቁ) እንደሚነሳ ብጤ እንጅ (ከመቃብራቸው) አይነሱም፡፡ ይህ እነርሱ መሸጥ የአራጣ ብጤ ብቻ ነው በማለታቸው ነው፡፡ ግን መሸጥን አላህ ፈቅዷል፡፡ አራጣንም እርም አድርጓል፡፡ ከጌታውም ግሳጼ የመጣለትና የተከለከለ ሰው ለርሱ (ከመከልከሉ በፊት) ያለፈው አለው፡፡ ነገሩም ወደ አላህ ነው፤ (አራጣን ወደ መብላት) የተመለሰም ሰው እነዚያ የእሳት ጓዶች ናቸው፡፡ እነርሱ በውስጧ ዘውታሪዎች ናቸው፡፡›› **(አልበቀራ፡ 275)**

በአላህና በመልክተኛው (ሰ.ዐ.ወ) ፊት እጅግ ፀያፍ ገንዘብ ማግኛ መንገድ ወለድ ነው፡፡[68]

ሰዎችን ከዚህ ከባድ ኃጢያት ለመታደግ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ወለድ የሚበሉትን፣ አዋዋዩንና ምስሮችንም ጭምር ረግመዋል፡፡

አንዳቸው ከሌላኛው የማይለዩ እኩል ኃጢያተኞች እንደሆኑ አስገንዝበዋል፡፡[69]

---

67 አል-በቀራ 2:278-279 የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) በተጨማሪ አላህ (ሱ.ወ) በእርሱ ጓደኞች ላይ ጥፋት ባወጁት ላይ ጦርነት እንዳነሳ ተናግረዋል፡፡ (ቡኻሪ፣ ረይቅ 38) ከዚህ ሁኔታ ውጪ የትኛውም ኃጢያተኛ ሆነ አመፀኛ በእዚህ ደረጃ ማስጠንቀቂያ አልተሰጠውም፡፡

68 ኢብን አቢ ሽይብ ሙስነፍ VII 106/34552፤ ሻኢድ III1016፣ ኢብ ከሲር ቢዳይ V 13-14

69 ሙስሊም ሙስካት 105-106፤በተጨማሪም ቡኻሪ ቢዕዩ 24 እና 25 እና 113፤ አቡዳውድ ቡዕይ 4/3333 ቲርሚዚ ቡዕዩ 2/1206፤ ኢብን ማዓስ፤ ቲጃራት 58 ይመልከቱ

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ይህንን ያመለከቱት ኢስላማዊ ማህበረሰብ ወለድን የሚታገስበትም ሆነ የሚያስተናግድበት ምንም አይነት ማዕቀፍ እንደሌለው በማያወላዳ መልኩ ግልፅ አድርገው ለማሳየት ነው፡፡ ወለድ በሁሉም ኃይማኖት ጭምር የተከለከለ ነው፡፡[70]

በአሁኑ ወቅት ከወለድ ነፃ የሆነ ኢኮኖሚ መመስረት አይቻልም ብሎ ማሰብ ስህተት ነው፡፡ ከወለድ ነፃ የሆነ ኢኮኖሚ መመሥረት በደንብ ይቻላል፡፡ ይህንን የኢኮኖሚ ስርአት የዘረጉና ስኬታማም የሆኑ ህብረተሰቦች አሉ፡፡ ኢስላም የወለድን የኢኮኖሚ ስርአት ሲከለክል አማራጩን አስቀምጦ ነው፡፡ ሽርክና አንዱ ነው፡፡ ብድርም ሌላው ነው፡፡ በሌላ በኩልም ዘካ እና ሰደቃ አሉ፡፡ ኢስላም ምሉእ የሆነ የኢኮኖሚ መረጋጋትና ሥርአት የሚመሠርት ነው፡፡

# አልኮል መጠጣት

የአልኮል መጠጦች ከሰው ተፈጥሮ ጋር የሚቃረኑ ጎጂ ነገሮች ናቸው፡፡ ትክክለኛ የሰዎች ሁኔታ ንቁነትና ጠንቃቃነት ነው፡፡ ስንፍናና ራስን መተው (መሳት)ፈፅሞ ተቀባይነት የላቸውም፡፡ ንቁነትን ማጣት በጥልቅ ስህተት ውስጥ የሚከት ነው፡፡ አልኮል መጠጣት ተፈጥሯዊ ነው የሚሉ ሰዎች ሊሸሽጉት ያልቻሉት ሐቅ ነው፡፡

አልኮል መጠጦች በጠጪውም ሆነ በማህበረሰቡ ላይ ለሚደርሰው ጠንቅ ዋና ምክንያት ናቸው፡፡ ይህች ዓለምም (ሕይወትም) ሆነ የመጪው ዓለም ሁኔታ የሚወሰነው በጠንቃቃ እንቅስቃሴ ሆኖ ሳለ የአልኮል መጠጦች የሰዎች የማሰብ አቅም ይነጥቃሉ፡፡ የሰዎችን አቅል ሲወሰድ (አቅላቸውን ሊስቱ) የማይታመኑ ስህተቶችን

---

[70] An-Nisâ (Women), 4: 160-161.

ይፈፅማሉ፡፡ አልኮል አሰቃቂና ዘግናኝ ኃሳቦች በሰው ጭንቅላት ውስጥ እንዲፈለፈሉና ጉልበት እንዲያገኙ ያደርጋል፡፡

በአልኮልና ቁማር አማካኝነት ሰይጣን በሰዎች መካከል ጭካኔና ጠላትን እንዲጠነሰስ ያደርጋል፡፡ አንዱን በሌላው ላይ ያስነሳዋል፡፡ አላህን ከማስታወስና ከማምለክ ሰዎች እንዲዘናጉ ያደርግና በዚህም በመጪውም ዓለም ያራቁታቸዋል፡፡ በአጭሩ ሰይጣን ይህንንም ሆነ መጪውን ዓለም ያጠፋባቸዋል፡፡[71]

ራሺያዊው ፕሮፌሰር ራቺንስኪ (Rachinsky) የሚከተሉትን ምርጥ ቃላት ተናግሯል፡፡ "ሰይጣን በጠርሙስ ውስጥ ይደበቅና ሱሰኞችን ያላቸውን በሙሉ ይወስድባቸዋል፡፡ ሌላው ይቅርና ገላቸው ላይ የቀረችውን ሸሚዝና የልጃቸውን ዳቦ ጭምር ይነጥቃል፡፡ በተጨማሪም ሰይጣን ጠጪዎችን ከሰዎችና ከቤተሰባቸው መሃከል ነጥቆ ባሪያ ያደርጋቸዋል፡፡ ጤናቸውን፣ ሥነ ምግባራቸውን፣ ህሊናቸውን፣ ሳቅና ፈገግታቸውን፣ መረጋጋታቸውንና ደስታቸውን ከጠጪዎቹ ላይ ጠራርጎ ያራግፈዋል፡፡ የመስራት ፍላጎትና ወኔን ስለሚሰብር ድህነት ውስጥ ይከታል፡፡ እስቲ የአልኮል መጠጦችን በማምረት በከንቱ የሚፈሰውን ጉልበት አስቡት፡፡ ምን ያህል የምግብ ንጥረ ነገሮች፣ ለመጠጥ የሚሆን ውሃ እንዲህ አይነት መጠጥ ለማምረት እንደሚባክን አጢኑት፡፡ ሰዎች በንዝህላልነት በአልኮል ኩሬ ውስጥ የሚጥሏቸው (የሚከቱዋቸው) በሚሊዮን ኩንታሎች የሚመዘኑ ስንዴ፣ ገብስ፣ ወይን ለረሀብተኞች ቢከፋፈሉ ኖሮ ምንም አይነት ሰው በረሃብ ባልሞተ ነበር፡፡ ከሰዎችም አልፎ ለእንሰሳቶች በተረፈ ነበር፡፡

"በጠርሙስ ለሚደበቀው ሰይጣን የተበጀተው በጀት መጠን በእግጠኝነት የሚያውቀው የለም፡፡ ምክንያቱም ሰይጣንን ለመከተል

[71] Al-Mâida (The Table), 5: 90-91.

የፈቀዱ ግብሩንም (Tax) ጭምር ለመክፈል ወደኋላ አይሉም፡፡ ነገር ግን እነዚሁ ሰዎች የተበደሩትን ለመክፈል ፈፅሞ ዳተኞች ናቸው፡፡ ሰይጣን ሁሌም ገቢውን የሚቀበለው ሳይጓደልበት በጥሬ ገንዘብ ነው፡፡ እነዚህ ሱሰኞች የሚገብሩበት ገንዘብ ከሌላቸው እንኳን ይሰርቃሉ፣ ይገድላሉ ወይም የራሳቸውንና የቤተሰቦቻቸውን ክብር ያዋርዳሉ እንጂ ግብሩን ከመክፈል ወደኋላ አይሉም፡፡

በአልኮል አማካኝነት እጅግ ውድ እና ድንቅ የሆኑ ሰዎች ሕይወት ጠፍቷል፡፡ እነዚህ ሰዎች ክብራቸው ተገፎ ቀለዋል፡፡ አልኮል በሚሊዮኖች የሚቆጠሩ ሰዎችን ጤና አውድሟል፡፡ ጠንካራ ሕንፃዎችን በውሃ ላይ መገንባት እንደማይቻለው ሁሉ፤ ጠጪ ሰዎችን ይዞ ኃያል አገርን መገንባት ፈፅሞ አይሞከርም፡፡ ስለዚህ የእድገት እንቅስቃሴ መጀመር ያለበት ይህንን ትውልድ ከዚህ አሰቃቂ ሁኔታ ከማውጣት ነው፡፡"[72]

የዓለም ጤና ድርጅት (WHO) 30 አገሮችን የተመለከተ በቅርብ ባወጣው ጥናት 85% የነፍስ ማጥፋት (ከነዚህ ውስጥ 60-70% የሚሆነው በቤተሰብ መካከል የተፈፀመ ነው)፣ 50% የወሲብ ጥቃቶች፣ 50% አሰቃቂ አደጋዎች፣ 70% የቤተሰብ ጥቃቶች፣ 60% ራስን የመዘንጋት በሽታ፣ ከ40-50% የአእምሮ ጤና መቀወስ ምክንያቱ መጠጥ እንደሆነ አሳይቷል፡፡ ከሱሰኞች የሚወለዱ ሕፃናት በአእምሮ በሽታ የመጠቃታቸው እድል 90% ነው፡፡ ሱሰኛ ሴት የምትወልደው ሕፃን በ35% አካል ጉዳተኛ የመሆን እድል አለው፡፡ ምክንያቱም አልኮል የማህፀን መዳበርን ያሳጥራል፣ የሽል እድገትን ያቀጭጫል፣ የአእምሮ ዝግመትን ያመጣል፣ ደዌን ያስከትላል፣ የባህሪ ችግርንም ይፈጥራል፡፡ ከጠጪ ቤተሰቦች መካከል የሚያድግ ሕፃን ዘወትር የሚመለከተው ጭቅጭቅና ድብድብ በመሆኑ ከፍተኛ

---

[72] Grigory Petrov, *Ideal ض ğretmen (The Ideal Teacher),* Istanbul2005, pp. 48-52.

የስሜት መድቀቅና የባህሪ ችግር ይጠናወተዋል። በመሆኑም እንዲህ አይነት ልጆች በየትኛውም የህይወት መስክ ስኬታማ የሚሆኑበት ዕድል እጅግ ጠባብ ነው።[73]

የእንግሊዝ መንግስት ባወጣው ኦፊሲሊያዊ ሪፖርት መሠረት በአልኮል መጠጥ ምክንያት የሚከሰቱ የሰዎች ብጥብጥ፣ አደጋዎች፣ የሆስፒታል ወጪና ሌሎች ተያያዥ ነገሮች በእንግሊዝ ኢኮኖሚ ላይ 20 ቢሊየን ፓውንድ (30 ቢሊዮን የአሜሪካ ዶላር) ኪሳራ ያደርሳል። [74]የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) "አልኮል (መጠጥ) በፍፁም እንዳትጠጡ፤ የከፋ ነገሮች ሁሉ እናት ነውና" ሲሉ አስጠንቅቀዋል። (ኢብን ማጃህ፣አሸሪባ፣1)

በተጨማሪም፡- “በብዙ ሲወሰድ (ሲጠጣ) አእምሮን የሚለውጥ ነገር፣ በትንሹም ቢሆን መቅመሱ ክልክል ነው" ብለዋል። (አቡ ዳውድ አሽሪባ 5/3861፣ቲርሚዚ፣አሽሪባ 3/1865)

"በትንሹ ፉት ማለት እኮ መስከር አይባልም" የሚለው አባባል በኢስላም ቦታ የለውም። ምክንያቱም ኢስላም በዚህ ጉዳይ ላይ ያስቀመጠው መስፈርት ግልፅ ነው። በብዙ ስትጠጡት የሚያሰክራችሁ (አእምሮዋችሁን የሚለውጥ) በትንሹ መቅመስ ክልክል ነው። ኢስላም ኃጢያትን (ወንጀልን) የሚከለክልበት ስልት ወደ ወንጀሉ (ኃጢያቱ) የሚያመሩትን መንገዶች በመዝጋት ነው። ወደ ተግባር ለመለወጥ ልፍስፍስ በሆኑ ንድፈ ኃሳባዊ መፍትሄዎች ላይ ጊዜውን አያጠፋም። ሰዎች ወደ ኃጢያቱ እንዳይደርሱ ተግባራዊ

---

[73] Musa Tosun, Article: “Icki” (Alcoholic Drinks), *Diyanet Islâm Ansiklopedisi - Encyclopedia of Islam (Republic of Turkey, Presidency of Religious Affairs)*, XXI, p.463.

[74] *The Guardian,* Saturday March 27 2004, “Sobering thoughts about a claim”, Sean COUGHAN.

ስልቶችን አቅርቧል። ሰውየው እነዚህን ሁሉ እንቅፋቶችን አልፎ ወንጀሉን ከሰራ ማስተማሪያ የሚሆኑ ቅጣቶችን አስቀምጧል።

## ዝሙት

ወሲባዊ ሕገወጥነት (ብልግና) እና ዝሙት በሰዎች ዘንድ፣ ከሥነ ምግባር አንፃር፣ በሕግ ሥርዓቶች እና መለኮታዊ ኃይማኖቶች ዘንድ ዘወትር የሚወገዙ ነገሮች ናቸው። ዝሙት ቤተሰብን የሚያፈርስ፤ ዝምድናን፣ ጉርብትናን፣ ወዳጅነትን የሚበጥስ፤ መንፈሳዊ እና ሥነ ምግባራዊ ማንነትን የሚያነቅዝ፣ የሕብረተሰቡን ሕልውና የሚፈታተን ነገር ነው። ሰዎችን ለዝቃጭ ስሜቶቻቸው ተገዢ የሚያደርግ በመሆኑ፣ የሰውን ክብር አውልቆ ጥሎ፣ ቀላል የሚያደርግ ነው።

ከዚህ ባሻገር ወሲባዊ ብልግናና ዝሙት የአካላዊ ጤናም ችግር ያመጣሉ። በዚህ ተግባር ላይ የተሳተፉ ሰዎች በግብረ ስጋ ለሚተላለፉ በሽተዎች (STD) የተጋለጡ ናቸው። እነዚህ ሰዎች በጨብጥ፣ ቂጥኝ ትንሽ ቀደም ብሎ በነበሩት ጊዜያቶች በዋነኝነት ሚጠቁ ሲሆን እስካሁን ድረስ ምንም አይነት መድኃኒት ያልተገኘለት ኤች አይ ቪ/ኤድስ በዚህ ዘመን በዋነኝነት እያጠቃቸው ያለ በሽታ ነው። የኤች አይ ቪ.ኤድስ ዋና መተላለፊያ መንገድ ህገወጥ የግብረ ስጋ ግንኙነት ነው።

ባሪያዎቹ በእንደዚህ አይነት መንፈሳዊ ሆነ አካላዊ በሽታዎች እንዳይጠቁ የሚሻው አላህ፣ ህገ ወጥ ወሲብ ማድረግ ይቅርና አጠገቡም ድርሽ እንዳንል አስጠንቅቆናል።

﴿ قُلْ تَعَالَوْا أَتْلُ مَا حَرَّمَ رَبُّكُمْ عَلَيْكُمْ ۖ أَلَّا تُشْرِكُوا بِهِ شَيْئًا ۖ وَبِالْوَالِدَيْنِ إِحْسَانًا ۖ وَلَا تَقْتُلُوا أَوْلَادَكُم مِّنْ إِمْلَاقٍ ۖ نَّحْنُ نَرْزُقُكُمْ وَإِيَّاهُمْ ۖ وَلَا تَقْرَبُوا

ٱلْفَوَٰحِشَ مَا ظَهَرَ مِنْهَا وَمَا بَطَنَ ۖ وَلَا تَقْتُلُوا۟ ٱلنَّفْسَ ٱلَّتِى حَرَّمَ ٱللَّهُ إِلَّا بِٱلْحَقِّ ۚ
ذَٰلِكُمْ وَصَّىٰكُم بِهِۦ لَعَلَّكُمْ تَعْقِلُونَ ﴿١٥١﴾ الأنعام: ١٥١

«ኑ፤ ጌታችሁ በእናንተ ላይ እርም ያደረገውን ነገር (በእርሱም ያዘዛችሁን) ላንብብላችሁ» በላቸው፡፡ «በእርሱ (በአላህ) ምንንም ነገር አታጋሩ፡፡ ለወላጆችም በጎን ሥራ (ሥሩ)፡፡ ልጆቻችሁንም ከድህንት (ፍራቻ) አትግደሉ፡፡ እኛ እናንተንም እነርሱንም እንመግባችኋለንና፡፡ መጥፎ ሥራዎችንም ከእርሷ የተገለጸውንም የተደበቀውንም ሁሉ አትቅረቡ፡፡ ያችንም አላህ እርም ያደረጋትን ነፍስ በሕግ ቢኾን እንጅ አትግደሉ፡፡ ይህን ታውቁ ዘንድ (አላህ) በእርሱ አዘዛችሁ፡፡» **(አንዓም፡ 151)**

﴿ وَلَا تَقْرَبُوا۟ ٱلزِّنَىٰٓ ۖ إِنَّهُۥ كَانَ فَٰحِشَةً وَسَآءَ سَبِيلًا ﴿٣٢﴾ الإسراء: ٣٢

"ዝሙትንም አትቅረቡ፤ እርሱ በእርግጥ መጥፎ ስራ ነውና፤ መንገድነቱም ከፋ!" (አል ኢስራ፡ 32)

የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) አላስፈላጊ እይታ ምን ያህል ለቀልብ ጎጂ እንደሆነ እንዲህ ሲሉ ተናግረዋል፡- "በተከለከሉ ነገሮች ላይ ማፍጠጥ የሰይጣን መርዛማ ቀስት ነው፡፡ ለአላህ ብሎ ከዚህ ተግባር የታቀበ፣ በቀልቡ ውስጥ የሚሰማን ጣፋጭ ኢማን ይሰጠዋል፡፡" ሐኪም IV፣ 349/7875፤ ሐይታሚ VIII፡63)

አስቀድሞ የመጠንቀቅ ፖሊስን በዋነኝነት የሚከተለው ኢስላም የዝሙት (ህገ ወጥ ወሲብ) ተግባር እንዳይፈፅም ቅድመ ጥንቃቄ አስቀምጧል፡፡ ወንዶችም ሆኑ ሴቶች የወሲብ ስሜት ቀስቃሽ አለባበሶችን እንዳይለብሱ፣ የወሲብ ስሜት የሚቀሰቅሱ ባህሪያትን አንዱ ለሌላው ያታ እንዳያሳይ በማድረግ፣ ወንድና ሴት ለብቻቸው ተገልለው እንዳይቀመጡ በመከልከል እና ሌሎችም እርምጃዎችን በመውሰድ፡፡ በዚህ ምክንያት የተቃራኒን ፆታ የወሲብ ስሜት የሚቀሰቅሱ አስተያየቶች አነጋገሮች ከልክ ያለፈ የተቃራኒ ፆታ

መቀራረብ የዝሙትን መንገድ ከሚያመቻቹ ተግባራት ጋር እኩል ተኮንነዋል። ቤተሰብና ሕብረተሰብ ልጆችን በማስተማር፣ ምክንያታዊ ነገር ከሌለ ወጣቶችን ቶሎ ማጋባት፣ ትዳርን ማቅለልና ኃይማኖታዊ ስነ ምግባራት ዕሴቶች ህያው ሆነው እንዲቆዩ ማድረግ ሌሎች እርምጃዎች ናቸው።

ከዚህ መረዳት እንደሚቻለው ኢስላም አጥፊዎችን የመቅጣት ሱስ የተጠናወተው ሳይሆን ለወንጀል መፈልፈያ ምቹ ከባቢን በማድረቅ ሰዎች የተረጋጋ እና ሰላማዊ ሕይወት እንዲኖሩ ምን ያህል ጥብቅ ፍላጎትና ፍቃድ እንዳለው ነው። በመሆኑም በረዥም የኢስላም ታሪክ ውስጥ በዝሙት ምክንያት ቅጣት የተፈፀመባቸው ሰዎች እጅግ ጥቂት ናቸው።

ከላይ ከተጠቀሱት ኃጢያቶችና ወንጀሎች በተጨማሪም ኢስላም ሚከተሉትን ዋና ዋና ወንጀሎች በፅኑ ከልክሏል። ግድያ፣ ጥንቆላ፣ በደል፣ወላጆችን አለመታዘዝ፣ ውሸት፣ ክህደት፣ ሀሜት፣ የወላጅ አልባ ልጆችን ሃብትና ንብረት መውሰድ፣ ልግጪያ፣ ስርቆት እና ቁማር።[75]

[75] ቡኻሪ ሸሃዳት 10፣ ሸሳያ 23፤ ሙስሊም፣ ቢር 55 እና 56፤ አቡ ዳውድ፣ አዳብ 35/4875፤ አሕመድ III, 154 እና 135 እንዲሁም ለተጨማሪ ዝርዝረ ጉዳዮች Murat Kaya,*Efendimiz'den Hayat ضİçüleri* (ከነብያችን ሕይወት መመሪያ) Istanbul 2007, pp. 308-458.ይመልከቱ.

## *አካባቢ፣ ንፅህና እና ውሃ*

### አካባቢ

አላህ (ሱ.ወ)፡- “በአካባቢያችሁ የሚገኙትን ነገሮች የሰጧችሁ እንድትጠቀሙባቸው ነው” ይላል፡፡ አምላክ ለሰጠን ስጦታ አመስጋኝ ሆነን እንድንቀርብ አካባቢያችንንና በውስጡ ያሉትን ነገሮች በኃላፊነት መጠቀም አለብን፡፡ አካባቢን ቸል ማለት ወይንም ማጥፋትና ማበላሸት ምስጋና ቢስነታችንን የሚያሳየን ብቻ ሳይሆን ጥፋቶችንም የሚጋብዝ ነገር ነው፡፡ አላህ (ሱ.ወ) ይህንን ይላል፡-

﴿ ظَهَرَ ٱلْفَسَادُ فِى ٱلْبَرِّ وَٱلْبَحْرِ بِمَا كَسَبَتْ أَيْدِى ٱلنَّاسِ لِيُذِيقَهُم بَعْضَ ٱلَّذِى عَمِلُوا۟ لَعَلَّهُمْ يَرْجِعُونَ ﴿٤١﴾ ﴾ الروم: ٤١

‹‹የሰዎች እጆች በሠሩት ኃጢኣት ምክንያት የዚያን የሠሩትን ከፊሉን ያቀምሳቸው ዘንድ መከራው በየብስና በባሕር ተገለጠ፤ (ተሰራጨ)፡፡ እነርሱ ሊመለሱ ይከጀላልና፡፡›› **(አርሩም፡ 41)**

ምንም እንኳን ቀደም ብሎ አላህ (ሱ.ወ)፡-

﴿ وَٱلسَّمَآءَ رَفَعَهَا وَوَضَعَ ٱلْمِيزَانَ ﴿٧﴾ أَلَّا تَطْغَوْا۟ فِى ٱلْمِيزَانِ ﴿٨﴾ ﴾ الرحمن: ٧ – ٨

‹‹ሰማይንም አጓናት፡፡ ትክክለኛነትንም ደነገገ፡፡›› ‹‹በሚዛን (ስትመዝኑ) እንዳትበድሉ፡፡›› **(አርረሕማን፡ 7-8)**

ብሎ ቢያዝም፤ የሰው ልጅ ትዕዛዙን ሊተገብር ባለመፍቀዱ ይኸው አሁን ዋጋውን እየከፈለ ይገኛል፡፡[76]

አንድ ሙስሊም በቀልቡ በሰፈነው መረጋጋትና ውበት ምክንያት ከሰዎች፣ እንስሶችና ተክሎች፣ እንዲሁም ህይወት ከሌላቸው ግኡዛን

---

[76] Ar-Rahman, 55: 7-8.

ሁሉ ጋር በመልካም ይናገራል፡፡ ማንንም ላለመጉዳት ይጠነቀቃል፡፡ አንድ ቀን በነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ፊት አንድ አስከሬን ሰዎች ተሸክመው አለፉ፡፡ ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) "አረፈ ወይም ተገላገሉት" አሉ፡፡ ሰሃባዎችም "የአላህ መልዕክተኛ ሆይ! አረፈ ወይ ተገላገሉት ሲሉ ምን ማለትዎ ነው?" ሲሉ ይጠይቁዋቸዋል፡፡ ነብዩም፡- "አንድ አማኝ ሲሞት ከዚህችም አለም ጭንቀትና ድካም ተገላግሎ ወደ አላህ እዝነት እየሄደ ነው፡፡ ኃጢያተኛ ወይም ጥሩ ያልሆነ ሰው ሲሞት ሰዎች፣ መሬቱ፣ዛፉና እንስሶቹ ተገላገሉ፤ ሰላማቸውንም አገኙ" ሲሉ መለሱ፡፡ ነሳዒና አሕመድ

ሰዎች ፍጥረታትን በየትም ቦታ ይሁን በማንኛውም ሁኔታ ከመረበሽ መታቀብ አለባቸው፡፡ ምድሩን፣ ውሃውን፣ አየሩን መበከል፤ የከተማውንና የገጠሩን ገፅታ ማበላሸት ከሰውነት የማይሄዱ፣ ከክብሩ ጋር ተቃራኒ ተግባሮች ናቸው፡፡ ለኛም ሆነ ለሌሎች አለማሰብ ነው፡፡

ሙስሊሞች ሌሎችን ከማስቸገር እና ተፈጥሮን ከማበላሸት እንዲታቀቡ ተምረዋል፡፡ አካባቢን መንከባከብና ንፅህናውን መጠበቅ የተሟላ አማኝ የመሆን ቅድመ መስፈርቶች ናቸው፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ሰዎችን ሊያውኩ የሚችሉት ነገሮችን ከመንገድ ማስወገድ የእምነት አካል እንደሆነ ተናግረዋል፡፡"[77] አላህ (ሱ.ወ) ሌሎችን ማስቸገርን እንደማይወድም አያይዘው አስጠንቅቀዋል፡፡ ሙአዝ ኢብን አነስ (ረ.ዐ) የሚከተለውን ገጠመኙን እንዲህ ያወሳል፡-

"ከአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ጋር በአንድ ዘመቻ ላይ አብሪያቸው ነበርኩ፡፡ ወታደሮች በአንድ ቦታ ተከማችተው መተላለፊያ መንገድ ጠፋ፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) መልዕክተኛ ላኩና የሚከተለውን መልዕክት አስነገሩ፡፡

[77] Muslim, Iman, 58.

“የሰዎችን መተላለፊያ የዘጋ ወይም ሰዎች እንዳይተላለፉ ያስቸገረ፣ ከጂሃድ የሚገኘውን ምንዳ አያገኝም'" (አቡዳውድ፣ጂሃድ88/2629፡ አሕመድ III፣441)

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ቦታዎችን ማጨናነቅ፣ መንገዶችን መዝጋት ወይም አንድን የአላህ ባሪያ (ለየትኛውም ምክንያት) ማስቸገር መለኮታዊ ምንዳ እንዳናገኝ እንቅፋት እንደሚሆኑ አሳስበዋል።

ስለዚህ አንድ አማኝ ነኝ የሚል ሰው በአደባባይ ቦታዎች ላይ ከመትፋት፣ የግብር ይወጣ በሆነ መንገድ ተሽከርካሪን ከማቆም ሆነ ተላላፊ መንገደኛን ከማስቸገር መታቀብ አለበት። ታዋቂ ፈረንሳዊ ፀሐፊ ሞንቴኝ (Montaigne) "ሙስሊም ቱርኮች ለእንስሳት ማረፊያና መታከሚያ የሚሆኑ ቦታዎችንና ሐኪም ቤቶችን እንደሰሩ” ፅፏል። በ17ኛው መቶ ክ/ዘመን የዑስማንያ (ኦቶማን) ኢምፓየርን የጎበኘው ጉየር (Guer) የተባለ ፈረንሳዊ የሕግ ሰው ሕሙማን ድመቶችና ውሾች የሚታከሙበት ሆስፒታል በደማስቆ እንደተመለከተ አውስቷል። ፕሮፌሰር ዶ/ር ሰባዒ የሚከተለውን አስፍሯል።

"በጥንታዊ የከተማ ግንባታ ፕላን የታመሙ እና የደከሙ እንሰሶች ህክምናና እንክብካቤ ቀለብ የሚገኙበት ቦታ ነበር። አረንጓዴ ሜዳ (በአሁኗ ደማስቆ የከተማ ቦታ ይባላል) አገልግሎት ጊዜያቸውን ጨርሰዋል ተብለው በባለቤቶቻቸው የተጣሉ የጋማ ከብቶች የሚያገኑበት ቦታ ነበር። የጋማ ከብቶቹ እስኪሞቱ ድረስ በቦታው ይቆያሉ።ድመቶችም የሚበሉባቸው፣ የሚያርፉባቸው እና የሚንሸራሸሩባቸው ቦታዎችም ነበሩ። በቀን ውስጥ በመቶዎች የሚቆጠሩ ድመቶች ወደነዚህ ቦታዎች በመምጣት ምግባቸውን ያገኙ ነበር።"

ለእንሰሶች እንዲህ አይነት አመለካከት ያለው ኢስላም፣ ለተክሎችም ተመሳሳይ ርህራሄ ያሳያል። የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ሲናገሩ "ነገ

የምፅዓት ቀን ነው ቢባልና አንዳችሁ በእጃችሁ ችግኝ ቢኖር ይትከላት" ብለዋል፡፡ (አህመድ III፣191፣183)

እጅግ የተከበረው የነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ጓደኛ አቡ ደርዳ አንድ ጊዜ ተክል እየተከለ በነበረበት ወቅት አንድ ሰው ይቀርበውና "አንተ የተከበርክ የአላህ መልዕክተኛ ወዳጅ ሆነህ ተክል በመትከል ተጠምደሀል" ይለዋል፡፡

አቡደርዳም (ረ.ዐ) የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) "አንድ ሰው ተክል ተክሎ የትኛውም የአላህ ፍጡር ከተከሉ ከተመገቡ እንደ ሰደቃ (ምፅዋት) ይቆጠርለታል ሲሉ ሰምቻለሁ" ይለዋል፡፡

በሌላ ንግግራቸው የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲህ ብለዋል፡- "አንድ ሰው ሰዎች የሚጠለሉበትን ዛፍ (ያለ በቂ ምክንያት) የቆረጠ፣አላህ በጭንቅላቱ ወደ ጀሀነብ ይጎትተዋል"

(አቡዳውድ አዳብ፣158-159 /5329/)

ተወዳጁ ነብይ (ሰ.ዐ.ወ) የሙስሊሞች ጦር ዛፍ እንዳይቆርጥ፣ ተክሎችን እንዳይጨፈጭፍ ከልክለዋል፡፡[78] የበኑ ሪሳ ነገድን ማሳ በተመለከተ "ከዚህ ማሳ ላይ አንድ ዛፍ የቆረጠ ሌላ አንድ ችግኝ ይትከል" ብለዋል፡፡[79] ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ሁሉንም ፍጡር የሚያከብርና ለሁሉም ፍጡር አዛኝ የሆነ ህብረተሰብ መፍጠር ችለው ነበር፡፡ አካባቢያቸውን እንዲጠብቁና እንዲንከባከቡ መክረዋል፡፡ የመጀመሪያው

[78] አቡ ዳውድ፣ መናሲክ 96፤ M. Hamidullah, *İslam Peygamberi* (የኢስላም ነብይ) Istanbul 2003, I, 500; a.mlf., *el-Vesâik,* Beirut 1969, ገጽ 236-238 እና 240 Ali Rıza Temel, "İslam'a Göre İnsan Çevre İlişkisi" (የሰውና አካባቢው ግንኙነት በኢስላም) ገጽ 77

[79] Belazuri, *Fütûhu'l-büldân,* Beirut 1987, p. 17; İbrahim Canan, *İslam ve Çevre Sağlığı* (ኢስላምና የአካበናቢ ሳይንስ) İstanbul 1987, ገጽ 59-60

ኸሊፋ አቡበክር (ረ.ዐ) ለዘመቻ የሚንቀሳቀሱ ወታደሮቹን ሲመክር እንዲህ ነበር ያለው፡-

"ቃላችሁን አትጠፉ፣ ምርኮኞችን አትዝረፉ፣ ጆሮ አትቁረጡ፣ አፍንጫ አትፎንኑ፡፡ ልጆችን፣ አዛውንቶችን፣ ሴቶችን አትንኩ፡፡፡ የተምር ዛፍ አትቁረጡ፣ አታቃጥሉ፣ ፍሬ የሚያፈራ ዛፍ እንዳትቆርጡ፡፡ ለምግብነት ከምትጠቀሙት ውጪ፣ በጎችን፣ ላሞችንና ግመሎችን እንዳታርዱ፡፡ በገዳም ውስጥ በአምልኮ የተጠመዱ መለኩሴዎችን ታገኛላችሁ፤ እንዳትነኳቸው..."[80]

ኮምቴ ዶ ቦኔቫል (Comte de Bonneval) የሙስሊሞችን ሥሡ ልብ ተመልክቶ እንዲህ ነበር ያለው "አቶማን ቱርኮች ፍሬ የማትሰጥን ተክል እንዳትጠወልግና እንዳትሞት ገንዘብ መድበውላት በየቀኑ ውሃ ሲያጠጡ መመልከት የተለመደ ነው፡፡"

## ፅዳት

ኢስላም አካላዊና መንፈሳዊ ፅዳትን ያበረታታል፡፡ ሰዎችንም ለዚህ ያተጋል፡፡ በቅዱስ ቁርአን እንዲህ የሚል ተፅፏል፡፡

﴿ وَيَسْـَٔلُونَكَ عَنِ ٱلْمَحِيضِ ۖ قُلْ هُوَ أَذًى فَٱعْتَزِلُوا۟ ٱلنِّسَآءَ فِى ٱلْمَحِيضِ ۖ وَلَا تَقْرَبُوهُنَّ حَتَّىٰ يَطْهُرْنَ ۖ فَإِذَا تَطَهَّرْنَ فَأْتُوهُنَّ مِنْ حَيْثُ أَمَرَكُمُ ٱللَّهُ ۚ إِنَّ ٱللَّهَ يُحِبُّ ٱلتَّوَّٰبِينَ وَيُحِبُّ ٱلْمُتَطَهِّرِينَ ﴿٢٢٢﴾ ﴾ البقرة: ٢٢٢

‹‹አላህ (ከኃጢአት) ተመላሾችን ይወዳል፤ ተጥራሪዎችንም ይወዳል በላቸው፡፡›› **(አል በቀራ፡ 222)**

---

80 Beyhaki, *es-Sünenü'l-kübrâ,* IX, 85; Ali el-Müttakî, *Kenz,*no: 30268; İbnü'l-Esîr, *el-Kâmil,* Beirut 1987, II, 200.

የአላህም መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ሲናገሩ "አላህ ንፁህ ነው፤ ንፅህናን ይወዳል" ብለዋል፡፡ (ቲርሚዚ አዳብ 41/2799)

የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ለሁሉም አይነት ንፅህና ትኩረት ሰጥተው እንደነበር በቀላሉ ማየት ይቻላል፡፡ ወደ መስጊድ ሲሄዱ፣ በአደባባይ ሲገኙ ሆነ ጓደኛ ሲጎበኙ ንጹህ ልብስ መልበሳቸውን፣ ሽቶ መቀባታቸውን፣ መጥፎ የአፍ ጠረን የሚያመጡ ምግቦችን አለመመገባቸውን ያረጋግጡ ነበር፡፡

አቡ ኩርሳፍ (ረ.ዐ) የሚከተለውን ይተርክልናል፡-

"እናቴ፣ አክስቴና እኔ ቃልኪዳናችንን ልንሰጥ ወደ አላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ሄድን፡፡ ጉዳያችንን ጨርሰን ስንመለስ እናቴና አክስቴ "ልጄ፣ እንደዚህ አይነት ሰው አላየንም ፊቱ እንደዚህ ውብ የሆነ፣ ልብሱ የፀዳ እና ቃላቱ ለስላሳ የሆነ ሰው አናውቅም፡፡ ከአፉ ብርሃን የሚፈልቅ ይመስላል" ብለዋል፡፡" (ሃይታሚ VIII 279-280)

ኢስላም በንፅህና እና የረድኤት መርህ ላይ የተመሠረተ ሥርዓት ዘርግቷል፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) "ንፅህና የእምነት ግማሽ ነው" ብለዋል፡፡[81] ሁሉም የኢስላም የሐዲስ፣ የህግና ስርአት መፅሐፍት የሚጀምሩት ስለ ንፅህና በሰፊው በማንሳትና በመዘርዘር ነው፡፡ በኃይማኖቱ አንዳንድ የአምልኮ ሥርዓቶች አካላዊና አካባቢያዊ ንፅህና ካልተጠበቀ ተቀባይነት የላቸውም፡፡ ገላ መታጠብ አፅንኦት ተሰጥቶታል፡፡ ነጃሳ (ቆሻሻ) ነገሮች በሙስሊም ልብስ ላይ እንዳይኖሩ ትዕዛዝ ተላልፎባቸዋል፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በዚህ ጉዳይ ላይ ተከታዮቻቸውን አስጠንቅቀዋል፡- "ከመቃብሩ ቅጣት መንስኤዎች

---

[81] Muslim, Taharah 1.

አብዛኞቹ የሽንትን ነጃሳነት ቸል ከማለት ጋር የተጓዘን ነው" ብለዋል፡፡[82]

ኢስላም የተወሰኑ የሰውነት ክፍሎችን በቀን ውስጥ ቢያንስ ለአንድ ጊዜ የማጠብን ግዴታ ጥሏል፡፡ እጅ፣ አፍ፣ ፊት፣ ጭንቅላት፣ ጆሮዎች፣ አንገት እና እግር ትጥበት ግዴታ የሆነባቸው ለቆሻሻ እና ተህዋሲያን የተጋለጡ የሰውነት ክፍሎቻችን ናቸው፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ሲናገሩ "የጀነት ቁልፍ ሶላት ነች፡፡ የሶላት ቁልፍ ደግሞ ንፅህና ነው" ብለዋል፡፡[83]በመሆኑም ኢስላም ለአምልኮ ቅድመ ሁኔታ የሚፈፀመውን ትጥበት የአምልኮ አካል አድርጎታል፡፡ ስለሆነም ሰዎች ንፁህና ሲፈፅሙ አምልኮ እየፈፀሙ እንደሆነ አስተምሯል፡፡

ሌላው የአላህ መልዕክተኛ ትኩረት የሰጡት ጉዳይ የአፍ ንፅህናን ነው፡፡ አንድ ሙስሊም ከኪሱ መፋቂያ (ሚስዋክ) እንዳይጠፋ፣ በተለይ ከውዱዕ በፊት ጥርስን በመፋቂያ እንድናፀዳ መክረዋል፡፡[84] ሙስሊሞች ከምግብ በፊትና በኋላ እጆችን በመታጠብ የምግብን በረካ እንዲጨምሩ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲሁ አስገንዝበዋል፡፡[85]

ተፈጥሮዋችንን በተመለከተ መገረዝ፣ የብልት ዙሪያ እና የብብት ፀጉርን መላጨት፣ ፂምን ማስተካከልና ቀድሞ ቀመሶችን መቀምቀም በነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) የተደነገጉ የመልካም ባህሪያት ንፅህና መገለጫዎች ናቸው፡፡[86]

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ስለ ንፅህና አትኩሮት እንደሰጡ ሁሉ ስለ ፅዳትና ሥርዓትም የዛኑ ያህል አፅንኦት ሰጥተዋል፡፡ አንድ ጊዜ መስኪድ

---

[82] Ibn-i Majah, Taharah, 26.
[83] Ahmad, III, 340.
[84] Bukhari, Jumuah, 8; Temenni, 9; Savm, 27; Muslim, Taharah,42.
[85] See Tirmizi, Et'ime, 39/1846.
[86] Bukhari, Libas, 63-64.

ተቀምጠው ሳለ አንድ ፀጉሩንና ፂሙን ያንጨባረረና ያዘበራረቀ ሰው ይገባል። ነብዩም በምልክት ፀጉሩንና ፂሙን እንዲያስተካክል ጠቁመውታል።[87]

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ልባሳቸው መጥፎ ጠረን እንዲኖረው አይፈቅዱም ነበር። በዚህም ምክንያት አንድ ልብሳቸውን ጥለዋል። ባለቤታቸው አይሻም (ረ.ዐ) ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ሽቶ በእጅጉ እንደሚወዱ ተናግራለች።[88]

የነብዩ ወዳጆች (ሶሃባዎች) ራሳቸውን ለመቻል የሚታገሉ ሰዎች ነበሩ። የጁመዓ ሶላት እስኪደርስ ድረስ ሲሰሩ ይቆዩና በቀጥታ ወደ መስጂድ ይመጡ ነበር። የሠወነታቸው ጠረን ይህንን ያሳብቅ ነበር። ታዲያ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) አንዴ "ለምን ዓርብ ገላችሁን አትታጠቡም" ሲሉ መከሯቸው። (የቡኻሪ፣ ጁምዓ 16፣ቡዩ 15፤ ሙስሊም ጁሙዓ 6)

ሙስሊሞች "ንፅህና የእምነት ግማሽ ነው"[89] የሚለውን የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ንግግር ድንቅ በሆነ የፅሁፍ ጥበብ ከሽነው፣ በፍሬም አድርገው በቤታቸውና መስጊዶቻቸው ግርግዳ ላይ ይሰቅላሉ። ታዋቂው የህንፃ ነዳፊ "ሚማር ሲናን" (Mimar Sinan) የሕዝብ ዕቃ ማጠቢያ፣ ውሃ ማቆያ፣ መጠጫ ፏፏቴዎችና የሕዝብ ገላ መታጠቢያ በኦቶማን ኢምፓየር በየጥጋ ጥጉ ገንብቶ ነበር። በሙስሊም ማህበረሰብ ውስጥ ንፅህና ፍጹም ደረጃ ላይ እንዲደርስ በማሰብ በገጠሮች ውስጥ ሳይቀር የህዝብ መታጠቢያ ቤቶችን በብዛት ይገነባ ነበር።

---

87 *Muvatta',* Shaar, 7; Beyhakî, *Shuab,* V, 225.

88 Abu Dawud, Libas, 19/4074.

89 Muslim, Taharah, 1.

የሙስሊም ቤት እጅግ ንፁህ ነው፡፡ ከነጫማቸው ወደ ቤት አይገቡም፡፡ በተፈለገው ቦታ እንዲሰገድ በማሰብ ሁሉም ቦታ ንፁህ ነው፡፡ "የሳሎን ውሻ" የሚባል ነገር የለም፡፡

ኤም ደ ቴቬኖት (M.de Thevenot) ስለ ሙስሊሙ ህብረተሰብ ንፅህና ይህን ይላሉ፡፡ "ቱርኮች ጤነኛ ሆነው ነው የሚኖሩት፡፡ ቢታመሙም አልፎ አልፎ ነው፡፡ እኛ አገር በስፋት የሚያጠቁን የኩላሊትና ሌሎች አደገኛ በሽታዎ ቱርኮችን አያጠቃቸውም፡፡ እንደውም በሽታዎቹ ከነመኖራቸውም አያውቁም፡፡ ለጤንነታቸው ዋና ምክንያት በየጊዜው ገላቸውን መታጠባቸውና በአመጋገባቸውና አጠጣጣቸው መካከለኛ መሆናቸው ነው፡፡ ጥቂት ነው የሚበሉት፡፡ ምግባቸው ክርስቲያኖቹ እንደሚበሉት የተለያዩ አይነት ትርኪ ሚርኪ የለውም፡፡"[90]

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ሰዎች በሚተላለፉበት መንገድ፣ በሚዝናኑበት ቦታ ላይ፣ በሚቀመጡበት ዛፍ ስር መሽናትን አጥብቀው ከልክለዋል፡፡ አንድ ጊዜ በመስጂድ ግድግዳ ላይ አክታ ተለጥፎ አዩና፤ አፀዱት፡፡ በፊታቸው ላይ የነበረው ንዴት በግልፅ የሚታይ ነበር፡፡[91]

በአንድ ንግግራቸው እንዲህ ብለዋል፡-

"የተከታዮቼ መልካምና መጥፎ ስራዎች እንዳይ ተደረግሁ፡፡ ከመልካም ስራዎቻቸው መካከል ከመንገድ ላይ የሚጎዳ ነገርን ማንሳት፣ ከመጥፎም ስራዎች ደግሞ በመስጊድ ውስጥ መትፋትና አለመጥረግ የገኙባቸዋል፡፡[92]

---

90 M. De Thevenot, *Relation d’un Vogaye Fait au Levant*, Paris,1665, p. 58.
Muslim, Mesajid, 52; Beyhaki, *es-Sunenu’l-kubrâ*, I, 255.

91 Muslim, Mesajid, 52; Beyhaki, *es-Sunenu’l-kubrâ*, I, 255.

92 Muslim, Mesajid, 58. At that time there were no rugs, carpets,and the like in the mosques and the floor was sand.For this reason there were some who spit on the ground.

ሐዲሱ ስለመትፋት በግልፅ ተናግሯል፡፡መስጂድ የአምልኮ ቦታ እንደመሆኑ ሰዎችም ሚሰባሰቡበት ነው፡፡ ለአምልኮ ቦታች ከፍተኛ ጥንቃቄ የሚያደርጉ አማኞች፣ ሰዎች ለሚተላለፉባቸው መንገዶች የዛኑ ያህል ጥንቃቄ ያደርጋሉ፡፡ እነዚህን ቦታዎች በንፅህና መያዝና ከጎጂ ነገሮች ማፅዳት ከኢስላም ትዕዛዞች አንዱ ነው፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በዚህ ጉዳይ ላይ ከፍተኛ አፅንኦት ሰጥተዋል፡፡ ዑመር (ረ.ዐ) አቡ ሙሳ ዓል አሽዓሪን የባስራ መሪ አድርጎ ሲሾሙ ከሰጧቸው ትዕዛዞች መካከል የመንገዶችን ንፅህን መጠበቅ አንዱ ነበር፡፡[93]

አንድ ዞሮስትሪያን (እሳት አምላኪ) ከአቡ ሐኒፍ ብድር ወስዶ ነበርና አቡ ሐኒፍ ሊቀበሉት ወደ ቤቱ ያመራሉ፡፡ ሰውየው ቤት በር ላይ ሲደርሱ ጫማቸውን ሲያራግፉ አዋራው የሰውየውን ግርግዳ አበላሽቶት ይመለከታሉ፡፡ ምን እንደሚያደርጉ ግራ የገባቸው አቡ ሐኒፍ ይህንን ያስባሉ፡- "እንዲህ ብተወው የሰውየውን ቤት አበላሸዋለሁ፡፡ ብጠርገው ደግሞ ቀለሙን አገፈዋለሁ፡፡"

አቡ ሐኒፍ የሰውየውን ቤት ያንኳኩና ለሰራተኛዋ “አቡ ሐኒፍ በር ላይ ቆሞ ይጠብቅሃል” ብለሽ ንገሪው ይሏታል፡፡ ሰውየው እንደመጣ ስለብድሩ አስቀድሞ ይናዘዝና ይቅርታ መጠየቅ ይጀምራል፡፡

አቡ ሐኒፍም "የብድሩን ነገር ተወው" ይሉትና ይልቁንም ግድግዳውን እንዴት ሊያፀዱት እንደሚችሉ ይጠይቁታል፡፡ እሳት አምላኪው በዚህ እጅግ ስለተነካ "መጀመሪያ የኔን ነፍስ ላፅዳ" አለና ሰለመ፡፡[94]

---

[93] Darimi, Muqaddime, 46.

[94] Fahruddin er-Razi, *Mefâtihu'l-Gayb (et-Tefsîru'l-Kebîr),* Beirut 1990, I, 192.

## ውኃ

ለንፅህና ውኃ መሠረታዊ ነገር ነው፡፡ ከዚህም የበለጠ የዓለማችን ህልውና የተመሰረተው በውኃ ላይ ነው፡፡ ውኃ ለህይወት፣ ህይወት ላላቸው ነገሮች ሁሉ መሠረት ነው፡፡ ቅዱስ ቁርአን እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَٱللَّهُ خَلَقَ كُلَّ دَآبَّةٍ مِّن مَّآءٍ فَمِنْهُم مَّن يَمْشِي عَلَىٰ بَطْنِهِۦ وَمِنْهُم مَّن يَمْشِي عَلَىٰ رِجْلَيْنِ وَمِنْهُم مَّن يَمْشِي عَلَىٰٓ أَرْبَعٍ يَخْلُقُ ٱللَّهُ مَا يَشَآءُ إِنَّ ٱللَّهَ عَلَىٰ كُلِّ شَيْءٍ قَدِيرٌ ﴿٤٥﴾ ﴾ النور: ٤٥

‹‹አላህም ተንቀሳቃሽን ሁሉ ከውሃ ፈጠረ፡፡ ከእነሱም በሆዱ ላይ የሚኼድ አልለ፡፡ ከእነሱም በሁለት እግሮች ላይ የሚኼድ አልለ፡፡ አላህ የሚሻውን ሁሉ ይፈጥራል፡፡ አላህ በነገሩ ሁሉ ላይ ቻይ ነውና፡፡›› **(ኑር፡ 45)**

﴿ أَوَلَمْ يَرَ ٱلَّذِينَ كَفَرُوٓا۟ أَنَّ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلْأَرْضَ كَانَتَا رَتْقًا فَفَتَقْنَٰهُمَا وَجَعَلْنَا مِنَ ٱلْمَآءِ كُلَّ شَيْءٍ حَيٍّ أَفَلَا يُؤْمِنُونَ ﴿٣٠﴾ ﴾ الأنبياء: ٣٠

‹‹እነዚያም የካዱት ሰማያትና ምድር የተጣበቁ የነበሩና የለያየናቸው መኾናችንን አያውቁምን? ሕያው የኾነንም ነገር ሁሉ ከውሃ ፈጠርን፡፡ አያምኑምን?›› **(አል-ነበያ፡ 30)**

አላህ (ሱ.ወ) ፍጡራን እንዲጠቀሙበት ለውኃ የተለየ ባህሪ ሰጥቶታል፡-

1.እጅግ ብዙ ኦርጋኒክና ኦርጋኒክ ያልሆኑ ቅንጣቶችን (Compounds) ማሟሟት ይችላል፡፡

2. የውሃ አብዛኛው ይዞታው ጠጣር (በረዶነት) ሳይሆን ፈሳሽ ነው፡፡ በዚህ ባህሪው ውኃ ወደ ጠጣርነት (በረዶነት) የሚለወጠው በባህር፣ በሃይቆችና በውቅያኖሶች ወለል አካባቢ ነው፡፡፡ ይህ ደግሞ በውሃ ውስጥ የሚኖሩ እንሰሶችና ተክሎች በበረዶ እንዳያሩና እንዳይደርቁ ይጠበቃሉ፡፡

3. ለውኃ የቀረበ ቅንጅት (Compounds) ኃይድሮጅን ሰልፋይ ($H_2S$) ነው። ይህ ደግሞ የውኃን ሁለት እጥፍ ሲከብድ፣ በመካከለኛ ሙቀት (Room temperature) 25 $^0$C ላይ የሚኖረው ይዞታ ጋዝ ነው። መርዛምና መጥፎ ጠረን ያለው ነው።[95]

በቅዱስ ቁርዓን ውስጥ ውኃ በተደጋጋሚ ተጠቅሷል። ዝናብ እንዴት እንደሚፈጠር፣ ደመናዎች ወደ ዝናብ እንዴት እንደሚለወጡ፣ ዝናብ እንዴት እንደሚዘንብ፣ በዚህም የደረቀ አፈር ህይወት እንዴት እንደሚዘራ፣ የከርሰ ምድር ውኃዎች፣ የውኃ ፅዳትና ስለ ቆሻሻ ውኃ ማጥራት ቅዱስ ቁርዓን በዝርዝር አብራርቷል።[96]

የእነዚህ ሁሉ ስጦታዎች አስፈላጊነትም ተወስቶ ዝናብ "እዝነት" በሚል ስምም ተጠርቷል።[97]

የውኃን ዋጋ የሚያውቁ ሙስሊሞች ለተጠሙ ውሃ ለማጠጣት ከፍተኛ አትኩሮት ይሰጣሉ። በተለይ ለሐጅ የመጡ ሰዎችን ውኃና ብርዝ ማጠጣት እጅግ የተከበረና የተወደደ ስራ አድርገው ነው የሚመለከቱት።

የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) አጎት የነበረው አባስ (ረ.ዐ) ጣኢፍ ውስጥ የወይን እርሻ ነበረው። ከመስለሙ በፊትም ሆነ በኋላ ከዚህ እርሻው ወይን ያመጣና ከዘምዘም ውሃ ጋር አድርጎ ለሐጃጆች ይሰጥ ነበር። ከእርሱ በኋላም ልጆቹና ልጅ ልጆቹ ቀጥለውበት ነበር።[98]

---

95 Docent Dr. Şakir Kocabaş, *Kur'ân'da Yaratılış (Creation inthe Quran),* Istanbul 2004, p. 157.

96 Light (An Nur), 24 : 4; Ornaments of Gold (Az Zukhruf), 43 : 11; The Troops (Az Zumar), 39:21; The Event (Vakia), 68-70; Those Who Drag Forth (An Naziat), 79:31; The Criterion (Furkan), 25:48

97 The Heights (Al Araf), 7:57; Councel (Shurah), 42:28.

98 Ibn-i Hisham, IV, 32; Ibn-i Sa'd, II, 137; Vakidi, II, 838.

አንድ ጊዜ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ውኃ እና ብርዝ በነፃ ወደሚታደልበት የካዕባ አካባቢ ይመጡና የሚጠጣ ካለ ይጠይቃሉ፡፡ አባስም (ረ.ዐ) ለልጁ "ፈድል፣ለእናትህ ንገራትና ንጹሁውን መጠጥ ለነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) አምጣላቸው” ይለዋል፡፡ ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) "ሰው ሁሉ እየጠጣበት ካለው ከዚህ ስጠኝ" ይሉታል፡፡ አባስም "የአላህ መልዕክተኛ ሆይ ሰዎች እጃቸውን ነክረውበታል" ይላል፡፡ ነብም (ሰ.ዐ.ወ) "ችግር የለውም፤ ሰው ሁሉ ከሚጠጣበት ስጠኝ" አሉ፡፡

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ሁሉም ሰው ከሚጠጣበት ከጠጡ በኋላ ወደ ዘምዘም ጉድጓድ አመሩ፡፡ የአባስ ቤተሰቦች ውኃ ከጉድጓድ እያወጡ ለሐጃጆች ያድላሉ፡፡ የአላህ መልዕክተኛም (ሰ.ዐ.ወ) "የአብዱል ሙጠሊብ ልጅ ሆይ! ውኃውን አውጡ፤ እየሰራችሁት ያለው ነገር የተቀደሰ ነው" ሲሉ አመሰገኗቸው፡፡ ከዚያም "እናንተ የምትሰሩትን ለመስራት በሚፈልጉ ሰዎች ባትከበቡ ኖሮ ገመዱን እንዲህ አድርጌ ይዤ (ወደ ትከሻቸው እያመለከቱት) እናንተ እንደምታደርጉት አደርግ ነበር፡፡" አሉ፡፡ (ቡኻሪ፤ሐጅ 95)

የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ውኃን ለተጠማ ማጠጣት ያለውን ዋጋ ሲያብራሩ እንዲህ ብለዋል፡፡ "በፍርድ ቀን፤ ለጀሃነብ የተወሰነበት ሰው ወደ ጀነት ከሚገባ ሰው ጋር ይገናኝና "እገሌ ሀይ! ውኃ ጠምቶህ ያጠጣሁህን ታስታውሳለህ? ይለዋል፡፡ እንዲያማልደውም ይጠይቀዋል፡፡ የዚህም ምልጃ ተቀባይነትን ያገኛል፡፡ ለጀሀነብ የተባለው ሶስተኛም ሰውም ለጀነት ከተባለ ሰው ጋር ይገናኝና "እገሌ ሆይ! የሆነ ሥራ (ጉዳይ) እንድፈፅምልህ የላከኝን አስታወስክ? የዛን ጊዜ ፈፅሜልህ ነበር፡፡" ይለዋል፡፡ ወደ ጀነት ሚገባው ሰው ያማልድለታል፡፡”  (ኢብን ማጃህ አዳብ 8)

የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ለሚጠጡት ውኃ ንፅህናና ለጣዕሙም አትኩሮት ይሰጡ ነበር፡፡ ጣዕሙ ምርጥ የሆነ ውሃ ያሉዋቸው ጉድጓዶችን ይመርጡ ነበር፡፡[99]

የውኃ ጉድጓዶችም እንዳይበከሉ ከልክለዋል፡፡[100] እንደዚሁም ሁሉ ኢስላም ውዱዕ ለማድረግና ለትጥበት ንጹህ ውሃን እንደ ቅድመ ሁኔታ አስቀምጧል፡፡ ቀለማቸው፣ ሽታቸውና ጣዕማቸው የተበላሸ (የተለወጠ) ለውዱዕና ለመጠጥ እንዳንጠቀም ከልክሏል፡፡ ውኃ እጅግ አስፈላጊ ነገር እንደመሆኑ፣ ለአጠቃቀማችንም ሆነ ለንፅህናው ከፍተኛ ጥንቃቄ ማድረግ አለብን፡፡

ሰዎችን፣ እንሰሶችን፣ ተክሎችንና አካባቢያችንን ማፍቀር (መውደድ) አለብን፡፡ ዓለማችንንና በውስጧ የያዘችውን ነገሮች መንከባከብ አለብን፡፡

ሌላው እዚህ ጋር መነሳት ያለበት ነጥብ ብክነት ነው፡፡ የተፈጥሮ፣ የከባቢ፣ የውሃ ብክነት፡፡ አላህ (ሱ.ወ) እንዲህ ይላል፡፡

﴿ يَٰبَنِيٓ ءَادَمَ خُذُواْ زِينَتَكُمۡ عِندَ كُلِّ مَسۡجِدٖ وَكُلُواْ وَٱشۡرَبُواْ وَلَا تُسۡرِفُوٓاْۚ إِنَّهُۥ لَا يُحِبُّ ٱلۡمُسۡرِفِينَ ٣١ ﴾ الأعراف: ٣١

‹‹የአዳም ልጆች ሆይ! (ኀፍረተ ገላችሁን የሚሸፍኑትን) ጌጦቻችሁን በመስገጃው ሁሉ ዘንድ ያዙ፡፡ ብሉም፤ ጠጡም፤ አታባክኑም፡፡ እርሱ አባካኞችን አይወድምና፡፡›› **(አል አዕራፍ፡ 31)**

[99] Ibn Hajer, *Isabah,* III, 615.
[100] Bukhari, Wudu, 68.

﴿ إِنَّ ٱلْمُبَذِّرِينَ كَانُوٓا۟ إِخْوَٰنَ ٱلشَّيَٰطِينِ ۖ وَكَانَ ٱلشَّيْطَٰنُ لِرَبِّهِۦ كَفُورًا ﴿٢٧﴾ ﴾
الإسراء: ٢٧

‹‹አባካኞች የሰይጣናት ወንድሞች ናቸውና:: ሰይጣንም ለጌታው ብርቱ ከሓዲ ነው:::›› (**አል-ኢስራእ፡ 27)**

﴿ وَهُوَ ٱلَّذِىٓ أَنشَأَ جَنَّٰتٍ مَّعْرُوشَٰتٍ وَغَيْرَ مَعْرُوشَٰتٍ وَٱلنَّخْلَ وَٱلزَّرْعَ مُخْتَلِفًا
أُكُلُهُۥ وَٱلزَّيْتُونَ وَٱلرُّمَّانَ مُتَشَٰبِهًا وَغَيْرَ مُتَشَٰبِهٍ ۚ كُلُوا۟ مِن ثَمَرِهِۦٓ إِذَآ
أَثْمَرَ وَءَاتُوا۟ حَقَّهُۥ يَوْمَ حَصَادِهِۦ ۖ وَلَا تُسْرِفُوٓا۟ ۚ إِنَّهُۥ لَا يُحِبُّ ٱلْمُسْرِفِينَ ﴿١٤١﴾ ﴾
الأنعام: ١٤١

‹‹እርሱም ያ ዳስ የሚደረግላቸውንና ዳስ የማይደረግላቸውን አትክልቶች የፈጠረ ነው:: ዘምባባንም (የተምርን ዛፍ) አዝመራንም ፍሬዎቹ የተለያዩ ሲኾኑ ወይራንና ሩማንንም (ቅጠላቸው) ተመሳሳይና (ጣዕማቸው) የማይመሳሰል ሲኾኑ (ፈጠረ):: ባፈራ ጊዜ ከፍሬው ብሉ:: በአጨዳውም ቀን ተገቢውን (ዘካ) ስጡ:: አታባክኑም:: እርሱ አባካኞችን አይወድምና::››

**(አልአንዓም፡ 141)**

የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲሁ ሲናገሩ "ብሉ፣ጠጡ፣ልበሱ እና ሰደቃ ስጡ፤ ነገር ግን አታባክኑ፤ አትኩሩም" ብለዋል:: (ቡኻሪ፣ ኢብን ማጃህ ሊባስ 23)

ውኃ ለማባከን የሚሰጥ ምክንያት የለም:: ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ሰዒድ (ረ.አ) ውኃ እያፈሰሰ ውድዑ ሲያደርግ ይመለከቱታል::

"ይህ ሁሉ ብክነት ምንድነው?" ሲሉ ጠየቁት:: ሰዒድም "ውዱዕ ሲደረግ ከውኃ ብክነት መጠንቀቅ አለብኝን? ሲል ይጠይቃቸዋል:: ነብዩም "አዎን፣ ወንዝ አጠገብ ብትሆን እንኳን" ሲሉ መለሱለት::: (ኢብን ማጃህ፣ ጦኃራ 48)

አላህን ለማምለክ ውዱዕ ሲደረግ እንኳን ውኃ ማባከን ከተከለከለ፣ በሌላ ሁኔታዎች ውስጥ ምን አይነት ጥንቃቄ ማድረግ እንዳለብን ግልፅ ነው።

# ምዕራፍ ሶስት

# ቅዱስ ቁርአን

## አወራረዱና ጥብቅነቱ

አላህ (ሱ.ወ) ቅዱስ ቁርአንን በአንድ ጊዜ ሳይሆን ከፋፍሎ አወረደው፡፡ ይህ ደግሞ ብዙ ምክንያቶች አሉ፡፡ የዚህ የቅዱስ ቁርዓን አወራረድ ሁኔታ ለሰው ልጆች የተለያዩ ጥቅሞችና ምቾቶች ሰጥቷል፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ብዙ የወሕይ ፀሐፊዎች ነበሩዋቸው፡፡ በአንዳንድ ዘገባዎች እንደተጠቀሰው እስከ 65 ይደርሳሉ፡፡ ወህይ ከአላህ (ሱ.ወ) ሲወርድላቸው ከጸሐፊዎቻቸው አንደኛውን ይጠሩና ያፅፉ ነበር፡፡[101]ፀሐፊዎቹ በወቅቱ በነበሩ የመጻፊያ መሣሪያዎች ተጠቅመው ወህዩን ከፃፈ በኋላ መልሰው ለነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ያነቡላቸው ነበር፡፡[102]

የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) የወረደላቸውን ወህይ መጀመሪያ ለወንዶች ካነበቡላቸው በኋላ ለሴቶቹ ያነቡላቸዋል፡፡[103] ሙስሊሞቹም ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) የወረደውን ወህይ ይሸመድዳሉ፡፡ በፅሁፍም የሚያስቀምጡ ነበሩ፡፡ የወረዱት አንቀጾች በየቀኑ በየአምስት የሶላት ወቅት ይነበባሉ፡፡ በረመዳን ወር ወቅት ደግሞ ነብዩና መልዓኩ

---

[101] Prof. Dr. M. M. el-A‘zami, *Kur’ân Tarihi (History of Quran),* pp. 106-107. Ibn-i Ishak, *Sîret,* p. 128.

[102] Bukhari, Fedailu’l-Kur’an, 4; Tirmizi, Menakıb, 74/3954;Ahmad bin Hanbal, V, 184.

[103] Ibn-i Ishak, *Sîret,* p. 128.

ገብርኤል ቢያንስ ለሁለት ጊዜ ይናበባሉ፡፡[104] በዚህ የመናበቢያ ወቅት የተወሰኑ ሰሃባዎች ተገኝተው እንዲከታተሉ ይደረጋል፡፡ በጅብሪልና በነብዩ መካከል ያለው ሁለተኛ ዙር የመናበብ ሂደት እንዳለቀ፤ ነብዩ ሙሐመድ (ሰዐ.ወ) ለዑበይ ሁለቴ ያነቡለታል፡፡[105]

ከዚህ በተጨማሪ ነብዩና ሰሃባዎች ቁርአንን በማስተማር ያላሰለሰ ጥረት ያደርጉ ነበር፡፡ በመሆኑም ቅዱስ ቁርአን እያንዳንዱ አንቀፅ የተረጋገጠ በመሆኑ በመጽሐፍ መልኩ ለመጠረዝ ዝግጁ ነበር፡፡[106]

## ተዓምራዊ ተፈጥሮው

እያንዳንዱ ነብይ ከተላከበት ወቅትና ተጨባጭ ሁኔታ አንፃር ተዓምር ያሳያል፡፡ በኢየሱስ (ዐ.ሰ) ጊዜ ገናና የነበረው ሁነት የህክምና ሳይንስ ያደገበት ነበር፡፡ በህብረተሰቡ ውስጥ ታዋቂ የነበሩ ሰዎች የህክምና ባለሙያዎች ነበሩ፡፡ በዚህ ምክንያት እጅግ የመጠቁ የህክምና ባለሙያዎችን አፍ ያስያዘ ተአምራት ኢየሱስ አሳየ፡፡ በአላህ ፍቃድ አይነ ስውራንን አበራ፣ ሙታንን አስነሳ፡፡ በነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ዘመን የሥነ ፅሁፍ አዋቂነትና ምጥቀት የተጋነነበት ወቅት ነውና በዚህ በኩል የየትኛውም ዘመን ቋንቋ ዓዋቂዎችን እጅ ያሰጠ መጽሐፍ፣ ቅዱስ ቁርአን ተሰጣቸው፡[107]

---

104 Bukhari, Bed’u’l-halk, 6; Fedailu’l-Kur’an, 7.

105 *Mukaddimetân,* pub. A. Jeffery, pp. 74, 227; Tâhir el-Cezâirî, *et-Tibyân,* p. 26.

106 In this matter the following books can be consulted: Prof .Dr. M. M. el-A‘zami, *The History of the Qur’anic Text from Revelation to Compilation: A Comparative Study with theOld and New Testaments,* Leicester: UK Islamic Academy, 2003; M. Hamidullah, *Kur’ân-ı Kerîm Tarihi (The History of the Noble Quran)* (Introduction Section of *Le Saint Coran*).

107 አል-አንከቡት 29፡50-51፤ ቡኻሪ፣ ዒታሲም 1፣ ፈዳይዒዱል ቁርአን 1፤ ሙስሊም፣ ኢማን 279. እስከ ምፅዓት ቀን ሕያው ተዓምር ሆኖ የሚቆየው ቅዱስ ቁርዓን በተጨማሪ፤ እንደ ቀደምት ነቢያት ሁሉ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) የሰሩዋቸው ነብያት አሉ፡፡ እነዚህ ተዓምራት

ሥነ ፅሑፋዊ ውበቱና አቀራረቡ፣ ሕግ አርቃቂነቱ፣ በውስጡ የያዛቸው መረጃዎችና ምስጢራትን መግለጡ በርግጥ ቅዱስ ቁርአንን ታላቅ ተዓምር ያደርገዋል፡፡[108]

ኢ- አማኒያን በቅዱስ ቁርአን አናምንም በማለታቸው አላህ (ሱ.ወ) ፈተናቸው፡፡ ከሁሉም ፍጡራን ጋር ተቀናጅታችሁ አስር ቃላት የምትሆን የቅዱስ ቁርአንን የምትመስል አንቀፅ እንኳን አምጡ አላቸው፡፡

﴿ وَإِن كُنتُمْ فِي رَيْبٍ مِّمَّا نَزَّلْنَا عَلَىٰ عَبْدِنَا فَأْتُوا بِسُورَةٍ مِّن مِّثْلِهِ وَادْعُوا شُهَدَاءَكُم مِّن دُونِ اللَّهِ إِن كُنتُمْ صَادِقِينَ ﴿٢٣﴾ فَإِن لَّمْ تَفْعَلُوا وَلَن تَفْعَلُوا فَاتَّقُوا النَّارَ الَّتِي وَقُودُهَا النَّاسُ وَالْحِجَارَةُ ۖ أُعِدَّتْ لِلْكَافِرِينَ ﴿٢٤﴾ ﴾ البقرة: ٢٣ - ٢٤

‹‹በባሪያችንም ላይ ካወረድነው በመጠራጠር ውስጥ ብትኾኑ ከብጤው አንዲትን ምዕራፍ አምጡ፡፡ እውነተኞችም እንደኾናችሁ ከአላህ ሌላ መስካሪዎቻችሁን ጥሩ፡፡ (ይህንን) ባትሠሩ ፈጽሞም አትሠሩትምና ያችን መቀጣጠያዋ ሰዎችና ድንጋዮች የኾነችውን እሳት ተጠበቁ፤ ለከሓዲዎች ተደግሳለች፡፡›› **(አል-በቀራ፡ 23-24)**

"ፈፅሞ አትሰሩትምና" የምትለዋ አባባል፣ እንደው ሰዎች አመጣን የሚሉት ነገር ካለ እንኳን ዳኝነቱን መስጠት የሚችለው ከሥህተት የጠራና የፍጹም ዕውቀት ባለቤት የሆነ አካል አላህ ነው ማለት ነው፡፡ በርግጥም ስለወደፊቱና ድብቅ ዓለማት በርግጠኝነት ሊናገር የሚችል ከአላህ በስተቀር ማንም የለም፡፡

---

በብዙ መጽሐፍ ተዘግበው ይገኛሉ፡፡ ለምሳሌ በይሐቂ፣ ደላይሉን ኑቢው (በሰባት ቅፆች) ቤይሩት 1985፣ Ebu Nuaymel-Isfahânî, *Delâilü'n-Nübüvve* (በ2 ቅፆች) Halep 1970-1972; Suyûtî, *Olağanüstü Y◌nleriyle Peygamberimiz* (አል ሐሳይሱል ኩብራ) (በ3 ቅፆች) Istanbul 2003; እና ባለ አንድ ሺ.ህ ገጽ Nabhânî, *Hujjatullâh 'alâ al-âlamîn bi-mu'jizât Sayyid al-Mursalîn*.

[108] Prof. Dr. M. S. R. el-Bûtî, *Min Ravâi'ı'l-Kur'ân,* p. 125.

ይህ ፈተና በእርግጥ ለኢ-አማኒያን ደካማነታቸውን ያረዳቸው ነበርና ቃላቱ እረፍት ነስተዋቸዋል፡፡ እስካሁን ይህንን ፈተና ለማለፍ ሞክረዋል፤ በአሰቃቂና አስፈሪ ሁኔታ ወድቀዋል፡፡ ይህ አንቀፅ የኢአማንያንን ደካማነት ከምላስ ወደ ምላስ፤ አፅናፍ አፅናፍ የናኘ ነውና ደካማነታቸው በሰዎች ልብ ውስጥ፣ በራሳቸውም ጭምር ላይፋቅ ተቀርጿል፡፡[109]

ለዚህ መለኮታ ፈተና የኢአማኒያን ምላሽ ግን ፈፅሞ ሌላ ነበር፡፡ ስድብ፣ ማንጓጠጥ፣ የሐሰት ውንጀላዎች ነበሩ፡፡

﴿ وَقَالَ ٱلَّذِينَ كَفَرُواْ لَا تَسۡمَعُواْ لِهَٰذَا ٱلۡقُرۡءَانِ وَٱلۡغَوۡاْ فِيهِ لَعَلَّكُمۡ تَغۡلِبُونَ ٢٦ ﴾ فصلت: ٢٦

‹‹እነዚያም የካዱት «ይህንን ቁርኣን አታዳምጡ፡፡ ታሸንፉም ዘንድ (ሲነበብ) በእርሱ ውስጥ ተንጫጩ» አሉ፡፡›› **(ፉሲላት፡ 26)**

ሸንፈታቸውን የአደባባይ ሚስጢር ያደርግባቸው ነበር፡፡ ቅዱስ ቁርአን የግጥምም የቅኔም መጽሐፍ አይደለም፡፡ ነገር ግን ሁለቱን ያቀናጀ ፈፅሞ የተለየ ዘዬ ያለው መጽሐፍ ነው፡፡ በግጥም ሆነ በሙዚቃ ውስጥ የማይገኝ ውበት የያዘ ጥዑም ነው፡፡ ተደጋግሞ ቢነበብ አንባቢውንም ሆነ አድማጩን የማያሰለች፤ ነገር ግን በየቅፅበቱ በሚጨምር ፍስሀ ውስጥ የሚያሰጥም ነው፡፡[110]

ቅዱስ ቁርአን ልብን ቆንጥጦ የሚይዝ ነው፡፡ ሰዎችን ቁርአንን አታዳምጡ እያሉ ሲከላከሉ የነበሩ ሶስቱ ቀንደኛ ጠላቶቹ አቡ ሱፈያን፣ አቡ ጀህልና አኽነስ ቢን ሻሪቅ አንዱ ለሌላው ሳይናገር የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ቁርአን ሲያነቡ ለማድመጥ ጨለማን ተገን አድርገው በአንድ ቦታ ታደሙ፡፡ አድምጠው ሲመለሱ መንገድ

---

[109] M. S. Râfi'î, *I'câzü'l-Kur'ân,* Beirut 2003, p. 142.

[110] Prof. Dr. M. A. Drâz, *en-Nebeü'l-Azîm,* Dâru'l-kalem, ts., p. 102.

ላይ ሲገናኙ አንዱ ሌላውን ቢወቅስም ለሶስት ተከታታይ ቀናት ደጋግመው መምጣታቸውን አላቆሙም፡፡

በሶስተኛው ቀን ግን "ይህን ጉዳይ ለማንም አንነግርም፡፡ ሰዎች ስለ ሁኔታችን ቢያውቁ በአላህ ይሁንብን ያዋርዱናል፡፡ ብንናገርም የሚሰማን እናጣለን" ተባብለው ከተወቃቀሱ በኋላ በዛው ቀሩ፡፡[111]

ቅድስ ቁርአን የተለያዩ ሰዎችን ባሉበት የጊዜና የቦታ ተጨባጭ እንዲሁም የእውቀት ደረጃ የሚያናግር መጽሐፍ ነው፡፡ በመጀመሪያዎቹ ትውልዶች ዘንድ ባሉበት ተጨባጭ የተረዱትን አንቀጽ፣ በዚህ ዘመን የሳይንስና ቴክኖሎጂው እድገት በመጠቀበት ወቅት ያሉ ሰዎች መረዳት ይችላሉ፡፡ ታላቁ የአረብ ፀሐፊ ሙስጠፋ ሳዲቅ አርራፊ (Mustafa Sadik er-Raffi) እንዲህ ይላል፡- "ከቅዱስ ቁርአን ተዓምራት መካከል አንዱ በሁሉም ዘመናት ነዋሪ በሆኑ ሰዎች በሚታወቁ ቃላት ጊዜያቸው ሲመጣ የሚገለጡ እውነቶችን መያዙ ነው" (Wahy ul Kalem, Kuait ts, II,66)

## (ሀ) ስለማይታወቁ ነገሮች ይነግረናል

ቅዱስ ቁርአን ስለማይታወቁ ነገሮች ወሬ ይነግረናል፡፡ ይህ መረጃ ግልፅ ተአምር ነው፡፡ ስለተለያዩ ወደፊት ስለሚከሰቱ አካዳሚያዊ (ምሁራዊ) እና ሳይንሳዊ ጉዳዮች የሚናገር ቢሆንም አንድም ግኝት ግን ሊያስከልሰው አልቻለም፡፡ እጅግ የተደነቁና ታላላቅ ባህረ ዕውቀት መፅሐፍት (ኢንሳይክሎፒድያ) የተለያዩ ቅፆችን በመጨመር አትሞችን በማዘጋጀት ዳግም ይታተማሉ፡፡

---

111 ኢብን ሒሻም I, ገጽ 337-338፤ ጦበሪ፣ ታሪህ (ታሪክ)II, ገፅ 218-219፤ ኢብን አሲር፤ ካሚል II,ገፅ 63-64 ኢብን ሰይድ አልናስ፣ ዐይጉል አስር I, ገፅ 99፤ ዘይቢ፣ ታሪህል ኢስላም (የኢስላም ታሪክ) ገፅ 160-161፤ ኢብን ከሲር፣ አል ቢዳይIII,ገፅ 47፤ ሐሲቢ፣ ኢንሳጉል ዐዩንI, 462

ቅዱስ ቁርአን በወረደበት ወቅት ስለ አድ እና ሰሙድ ህዝቦች እንዲሁም ስለ ኖህ ውሃ ጥፋት ያሉት መረጃዎች ብጥስጣሽ ከመሆናቸው ባሻገር ከአፈ ታሪክነት የዘለሉ አልነበሩም፡፡ ነገር ግን ቅዱስ ቁርአን በዚህ ዘመን የታሪክ እውቀትና ፍልስፍና የተረጋገጡ መረጃዎችን ስለነዚህ ክስተቶች ተናግሯል፡፡

ስለመጪ ጊዜ ታሪካዊ ክስተትም ቅዱስ ቁርአን ይናገራል፡፡ የተወሰኑትን እንጥቀስ፡-

በሮማውያንና በዞሮስትያን መካከል ተደጋጋሚ ጦርነቶች ይካሄዱ ነበር፡፡ ኢስላም በአረቢያ መሰበክ በጀመረበት ወቅት ዞሮስቶሪያኖች ሮማውያኖቹን አሸንፈው ነበር፡፡ ይህንን አጋጣሚ ለመጠቀም የፈለጉ ኢ-አማኒያን ለሙስሊሞቹ " መለኮታዊ መፅሐፍ ስለተያዘ ማሸነፍ የምትችሉ ይመስላችሁ ነበር፡፡ አያችሁ ዞሮስቶራውያኑ የመጽሐፉ ባለቤት የሆኑትን ሮማውያኖቹን አሸነፉ" ብለዋቸው ነበር፡፡ እምነታቸውንና ስነ ልቦናቸውን ለመስበር አስበው ነበር፡፡ አላህ (ሱ.ወ) ግን አማኞችን ያስደሰተ ኢአማኒያንን ያስደነገጠ አንቀጽ አወረደ፡፡

١ غُلِبَتِ ٱلرُّومُ ٢ فِيٓ أَدۡنَى ٱلۡأَرۡضِ وَهُم مِّنۢ بَعۡدِ غَلَبِهِمۡ سَيَغۡلِبُونَ ٣ فِي بِضۡعِ سِنِينَۗ لِلَّهِ ٱلۡأَمۡرُ مِن قَبۡلُ وَمِنۢ بَعۡدُۚ وَيَوۡمَئِذٖ يَفۡرَحُ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ٤ بِنَصۡرِ ٱللَّهِۚ يَنصُرُ مَن يَشَآءُۖ وَهُوَ ٱلۡعَزِيزُ ٱلرَّحِيمُ ٥ الروم: ١ - ٥

‹‹አ.ለ.መ (አሊፍ ላም ሚም)፡፡›› ‹‹ሩም ተሸነፈች፡፡›› ‹‹በጣም ቅርብ በሆነችው ምድር፡፡ እነርሱም ከመሸነፋቸው በኋላ በእርግጥ ያሸንፋሉ፡፡›› ‹‹በጥቂት ዓመታት ውስጥ (ያሸንፋሉ)፡፡ ትዕዛዙ በፊትም በኋላም የአላህ ነው፡፡ በዚያ ቀንም ምእመናን ይደሰታሉ፡፡›› ‹‹በአላህ እርዳታ (ይደሰታሉ)፡፡ የሚሻውን ሰው ይረዳል፤ እርሱም አሸናፊው አዛኙ ነው፡፡›› **(አርሩም፡ 1-5)**

በዚያን ወቅት ባዛንታይኖች ክፉኛ ተጎድተው ስለ ነበር ዳግም ያንሰራራሉ ብሎ የገመተ ማንም አልነበረም፡፡ ነገር ግን አላህ “ሮሞች ያሸንፋሉ” ሲል ተናገረ፡፡

በርግጥም አላህ (ሱ.ወ) ቃሉን የሚጠብቅ ጌታ ነውና ቃሉ ተፈፀመ፡፡ በሁሉም የታሪክ ምሁራን በተመሠከረለት ሁኔታ በ9 ዓመት ውስጥ ሮማውያኑ ፋርሶቹን አሸነፉ፡፡ በዚያን ወቅት ሙስሊሞች የበድርን ጦርነት ድል ደስታ እያጣጣሙ ነበር፡፡[112]

አላህ (ሱ.ወ) በቀይ ባህር ተውጦ በጭንቅ ውስጥ ሲተናነቅ ለነበረው ፈርዖን እንዲህ ነበር ያለው፡፡

﴿ ءَآلۡـَٔـٰنَ وَقَدۡ عَصَيۡتَ قَبۡلُ وَكُنتَ مِنَ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ۝٩١ فَٱلۡيَوۡمَ نُنَجِّيكَ بِبَدَنِكَ لِتَكُونَ لِمَنۡ خَلۡفَكَ ءَايَةٗۚ وَإِنَّ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلنَّاسِ عَنۡ ءَايَٰتِنَا لَغَٰفِلُونَ ۝٩٢ ﴾ يونس: ٩١ - ٩٢

‹‹ከአሁን በፊት በእርግጥ ያመጽክ ከአጥፊዎችም የነበርክ ስትሆን አሁን (አመንኩ ትላለህ)?›› ‹‹ዛሬማ ከኋላህ ላሉት ተዓምር ትሆን ዘንድ በድን ሆነህ (ከባሕሩ) እናወጣሃለን (ተባለ)፡፡ ከሰዎችም ብዙዎቹ ከተዓምራታችን በእርግጥ ዘንጊዎች ናቸው፡፡›› **(ዩኑስ፡ 91-92)**

የፊርዐዎን እሬሳ በቅርቡ ተገኝቷል፡፡ ፀጉሮቹ ያልተነቃቀሉ እና ቆዳውም ያልተበላ ሲሆን በሱጁድ ሁኔታ ላይ ነበር፡፡ በለንዶን በሚገኘው የብሪቲሽ ሙዚየም 94ተኛው አዳራሽ ውስጥ ማየት ይቻላል፡፡

112 See Tirmizî, Tefsîr, 30/3191-3194; Ahmad bin Hanbal, I, 276; Kurtubî, XIV, 3.

## (ለ) ሳይንሳዊ ግኝቶች

ቅዱስ ቁርአን ስለ ሳይንስ እድገትና ግኝት የሚያወሱ ብዙ አንቀፆች አሉ። እነዚህ አንቀፆች ስለወደፊቱ ተናጋሪዎች እንደሆኑ ማየት ይቻላል። የኢስላም ዋና ዓላማ በሰዎች ልብ ውስጥ የአላህን አንድነት ማስረፅና ወደ ቀጥተኛ መንገድ መምራት ነው። የሚዳስሳቸው ርዕስ ጉዳዮች በሙሉ ከዚህ ገዢ አላማ ጋር የተያያዙ ናቸው። የተፈጥሮ ሳይንስን የተመለከቱ አንቀፆችን የያዘው ለሰዎች ትምህርት እንዲሆኑ በማሰብ ጭምር ነው። ሆኖም ግን ሁሉም ከሳይንሳዊ መረጃዎች እና ግኝቶች ጋር የሚሰናሰሉ የቁርአንን መረጃ የሚያረጋግጡ ናቸው። ምሳሌዎችን እንጥቀስ፡-

ቅዱስ ቁርአን የሰውን ልጅ የዘር ዑደት እና ሽል አፈጣጠር በተመለከተ የቅርብ ጊዜ ሳይንስ የደረሰበትን ዝርዝር መረጃ አቅርቧል።[113]

ስለ ሽል ጥናት በፃፈው ፅሁፍ ውስጥ ፕሮፌሰር ኪት ኤል ሙር (Prof. Dr.Keith L. Moor) የሽል እድገትን በዝርዝር ካቀረበ በኋላ ቅዱስ ቁርአን ካቀረበው ጋር በማወዳድር የሚከተለውን ማጠቃለያ ሰጥቷል። "ሳይንስ ከቅዱስ ቁርአን ገላፃ ጋር ሚስማማ ሲሆን እንደውም ቅዱስ ቁርአኑ የህክምና ሳይንስን በተመለከተ ባቀረበው ዝርዝር እና ምሳሌዎችን ዘመናዊ ሳይንስን ቀድሟል።"

ከጥናቱ በኋላ ዶ/ር ሙር ለቅዱስ ቁርአንና ለነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ያለውን ታላቅ አድናቆት ከመግለጹም በላይ፣ ከ1400 ዓመታት በፊት ለተገለጠው ቅዱስ ቁርአን ተአምራዊነት ጥልቅ ምስክርነቱን ሰጥቷል። Before we are Born በሚለው ሁለተኛ እትም መፅሐፍ ከቅዱስ ቁርአን ያገኘውን ትምህርት አካቷል። ታዲያ

---

113 Al-Hajj (The Pilgrimage), 22: 5; Al Mu'minûn (The Believers), 23: 11-13.

"የዚህን መረጃ በቅዱስ ቁርአን ውስጥ መገኘት እንዴት ታስረዳዋለህ?" ተብሎ ሲጠየቅ እንዲህ ነበር የመለሰው "ቅዱስ ቁርአን ምንም ሳይሆን ከአላህ የተወረደ ነው።"[114]

በቅርብ ጊዜ ዩንቨርሱን የተመለከተ አንድ ግኝት ተገኝቷል። በዩኒቨርሱ ውስጥ ያሉት ጋላክሲዎች እጅግ ፈጣን በሆነ ፍጥነት እየተራራቁ ነው። በዚህ በቅርብ በተገኘው ግኝት መሰረት እነዚህ ግዙፍ ጋላክሲዎች እንደየሚገኙበት ርቀት መጠን በሆነ ተዛምዶሻዊ ፍጥነት ይርቃል። ለምሳሌ ከእኛ በ10 ሚሊዮን የብርሃን ዓመት ርቀት የሚገኝ ጋላክሲ 250 ኪሎ ሜትር በሰኮንድ በሆነ ፍጥነት ይራራቃሉ። ሆኖም ግን ከኛ በ10 ቢሊዮን የብርሃን ዓመት ርቀት ላይ የሚገኝ ዩንቨርስ በ250.000 ኪሎ ሜትሮች በሰኮንድ ፍጥነት ይርቀናል።[115]

ይህ ሁኔታ በቅዱስ ቁርአን ውስጥ እንደሚከተለው ተጠቁሟል፡-

﴿ وَٱلسَّمَآءَ بَنَيۡنَٰهَا بِأَيۡيْدٖ وَإِنَّا لَمُوسِعُونَ ٤٧ ﴾ الذاريات: ٤٧

‹‹ሰማይንም በኀይል ገነባናት። እኛም በእርግጥ አስፋዋ ነን።››

**(አዝ ዛሪያት፡ 47)**

አዛኙና ታላቁ አምላካችን ዕድሜያቸውን ከጨረሱና ከሚፈነዱ ከዋክብቶች (Meteors) ይጠብቀናል። ጁፒተር ባለው ከፍተኛ ስበት፤ ሳተርን ደግሞ በበር ዘበኝነት ምድርን ሊያጠፏት ከሚችሉ የሰማያዊ አካላት ናዳ ይታደጉዋታል። አንዳንዴ እነዚህን ሁለት ፕላኔቶች አልፈው የሚመጡ ሜቴዮርስ አሉ። ጨረቃ ሌላ ዘብ ሆና ትጠብቃለች። ጨረቃ ምንም አይነት ከባቢ አየር ስለሌላት በገጽታዋ

114 Gary Miller, *The Amazing Qur'an,* pp. 34-39.

115 Prof. Dr. Osman Cakmak, *Bir Ɨekirdekti Kâinat (The Universe was a Seed),* p.28.

ላይ በግጭቶች ምክንያት የተፈጠሩ ትላልቅ ጉድጓዶች ይታያሉ። እነዚህ ጉድዶች መሬት ላይ ሆነን በአጉሊ መነፅር እንኳን ማየት ይቻላል። ጨረቃን ያለፉት ደግሞ ወደ ምድር ከባቢ አየር ሲገቡ መቃጠል ይጀምራ። ሜትዮርሶች እጅግ ግዙፍ ካልሆኑ በስተቀር የዝናብ ጠብታ ወደሚያካክሉ አቧራዎች ይለወጣሉ። ይህ የሜትርዮቶቹ ወደ አቧራነት የመለወጥ ክስተት በተለምዶ "ተወርዋሪ ኮከብ" የምንለው ነው።[116] ከባቢ አየር ምድርን ከነዚህ ሰማያዊ አካላት አደጋ ብቻ ሳይሆንም ከህዋ ከሚመጡ ጎጂ ጨረሮችም ይጠብቃታል። ቅዱስ ቁርአን ይህንን እውነታ እንዲህ ያስቀምጠዋል፦

﴿ وَجَعَلْنَا ٱلسَّمَآءَ سَقْفًا مَّحْفُوظًا ۖ وَهُمْ عَنْ ءَايَٰتِهَا مُعْرِضُونَ ﴿٣٢﴾ ﴾ الأنبياء: ٣٢

‹‹ሰማይንም (ከመውደቅ) የተጠበቀ ጣራ አደረግን። እነርሱም ከተዓምራቶቿ ዘንጊዎች ናቸው።›› **(አል-አንቢያ፡ 32)**

ቅዱስ ቁርአን በአንድ በኩል ስለ ሰዎች ባህሪና ድርጊት ሥርአት ሲናገር በሌላ በኩል ደግሞ ዩንቨርሱ የያዘውን ድብቅ ምስጢር (መረጃ) እየገለጠ ለጥናትና ምርምር የሚጋብዝ መጽሐፍ ነው።

ከአስራ አራት ምዕተ ዓመታት በፊት ቅዱስ ቁርአን እንዲህ ብሎ ነበር፦

﴿ وَأَرْسَلْنَا ٱلرِّيَٰحَ لَوَٰقِحَ فَأَنزَلْنَا مِنَ ٱلسَّمَآءِ مَآءً فَأَسْقَيْنَٰكُمُوهُ وَمَآ أَنتُمْ لَهُۥ بِخَٰزِنِينَ ﴿٢٢﴾ ﴾ الحجر: ٢٢

‹‹ነፋሶችንም (ደመናን) ተሸካሚዎች አድርገን ላክን። ከሰማይም (ከደመና) ዝናብን አወረድን። እርሱንም አጠጣናችሁ። እናንተም ለእርሱ አድላቢዎች አይደላችሁም።» **(አል ሒጅር፡ 22)**

116 Prof. Dr. Osman Cakmak, *Bir Çekirdekti Kâinat (The Universe was a Seed)*, pp. 94, 127.

ከምዕተ ዓመታት በኋላ በነፋስ አማካኝነት ተክሎችና ደመናት እንደሚዳብሩ በጥናት ተረጋገጠ።

"ሁለቱ ባህሮች የሚገናኙ ሲሆን ለቀቃቸው። (እንዳይዋሀዱ) በመካከላቸው ጋራጅ አለ፤ (አንዱ ባንዱ ላይ) ወሰን አያልፍም" **(አረ-ሕማን፡** 20)

﴿مَرَجَ ٱلْبَحْرَيْنِ يَلْتَقِيَانِ ۝١٩ بَيْنَهُمَا بَرْزَخٌ لَّا يَبْغِيَانِ ۝٢٠﴾ الرحمن: ١٩ - ٢٠

የሜዲትራኒያን ባህርና አትላስ ውቅያኖስ በሚገናኙበት የጂብራልታር ሰርጥ ሁለቱን ውሃዎች የሚከፍል ያልታወቀና የማይታይ መጋረጃ እንዳለ ሳይንስ አረጋገጠ። በዚህ መጋረጃ ምክንያት ሁለቱ የውሃ ክፍሎች የማይገናኙ ሲሆን የየራሳቸውን ባህሪይ እንደያዙ ጎን ለጎን ተቀምጠዋል። በኋላ ላይ ካፒቴን ጃኮስ ኮስታ (Capitain Jaques Cousteau) የተለያዩ ባህሪይ ያላቸው ባህሮች በሚገናኙበት ቦታ ሁሉ ይህ መረጃ እንዳለ አረጋገጠ።[117]

የቅዱስ ቁርአን ተዓምር በዚህ የሚያበቃ አይደለም። በውስጡ የያዛቸው ህግጋት በሁሉም ዘመን በየትኛውም ቦታ ላሉ ሕዝቦች የሚሆን ነው። የትኛውም ሰው ሆነ ሕሊና ሊያሂሰው የሚችል አይደለም። ሌሎች የህግ ስርአቶችን የሚያስጨንቃቸውን ተቃርኖ የፈታ ነው። ህግጋቱ በውስጣቸው የያዙት ታላቅ ጥበብ፤ ፍፁም የሆነ ማህበራዊና ፖለቲካዊ ሥርአት እንዲይዝ ስላደረገው ኢስላማዊ ስልጣኔ ወደቀ ሲባል ደግሞ እንዲያንሰራራ የሚያደርግ ነው። ይህ ደግሞ በየትኛው ስልጣኔ የማይታይ ነው።

---

117 ቁርአንና ሳይንስ በሚለው ርዕስ ላይ የበለጠ ለማወቅ የ Dr. Maurice Bucaille, *La Bible le Coran et la science: les ecritures saintes examinees a la lumiere des connaissancesmodernes,* Paris: Seghers, 1980 (*The Bible, the Qur'an andscience,* trc. Alastair D. Pannell, Karaçi, t.y.); Afzalurrahman,*QuranicSciences*,London1981;http://www.islamiyayinlar.net/content/view/106/8/.

የሕዝቦች ዕጣ ፈንታ ከፍፁም መሐይምነትና ጨለማ ውስጥ መንከራተት በሆነበት ወቅት ፊደል ባልቆጠሩና ባልተማሩ ነብይ አማካይነት 23 ዓመታት በፈጀ ጊዜ ውስጥ ዓለም ዳግም ወደ ቀድሞዋ ላትመለስ በብርሃን ተሞላች፡፡

# ምዕራፍ አራት

## የእዝነት ነብይ፣ ሙሐመድ ሙስጠፋ (ሰ.ዐ.ወ)

## የልጅነት እና የወጣትነት ጊዜያቸው

የአላህ መልዕክተኛ እንደ አውሮፓውያን አቆጣጠር በ571፣ በኢስላማዊ የጨረቃ አቆጣጠርበወርሐ ረቢአል አወል በ12ኛው ቀን በዕለተ ሰኞ ወደ ምድራችን መጥተው በበረከት ሞሏት፡፡ በእናታቸውም ሆነ በአባታቸው ከተከበረው የቁረይሽ ነገድ ነበሩ፡፡

የነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) የልጅነትና ወጣትነት ጊዜ ወደፊት የሚጠብቃቸውን ብሩሁን ዘመን የሚያመለክት ነበር፡፡ የእረኝነት፣ ከዚያም የንግድ ንፁህና ምርጥ ጊዜ አሳልፈዋል፡፡[118] በሐቀኝነታቸውና በሚዛናዊነታቸው ታዋቂ ለመሆን የበቁ፤ በዚህም ባህሪያቸው የተከበሩና የተፈቀሩ ነበሩ፡፡

ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ከሰዎች ሁሉ ምርጥ ነበሩ፡፡ በፅድቅና ከማንም የበለጡ፤ የሥነ ምግባር ማማ ላይ የተቀመጡ አንጸባራቂ ፈርጥ ነበሩ፡፡ የጎረቤቶቻቸውን መብት የጠበቁ፣ ፍፁም ታማኝና ትሁት የነበሩ፣ ከመጥፎ ባህሪያትና ሥራ የተጠበቁ ነበሩ፡፡ አንድንም ሰው ሲሰድቡ ሆነ ሲያንጓጥጡ አልተደመጡም፤ በክፉ ምላስም ሆነ በአካል አንዱንም ሰው ሲጎዱ አልታዩም፡፡ አምላክ ምርጥ ሰብዕናን ሁሉ ላበሳቸው በመሆኑ በመካ ሰዎች ዘንድ "ሙሐመድ አል ኢማን" (ሙሐመድ ታማኙ) በመባል ነበር የሚታወቁት፡፡ ከልጅነታቸው ጀምሮ በዚህ ስም ነበር የሚጠሩት፡፡[119]

---

118 Bukhari, Icâre, 2; Abû Dâwud, Edeb, 17, 82; Hâkim, III,200.

119 Ibn-i Hişâm, I, 191; Ibn-i Sa'd, I, 121, 156.

ሌላው ይቅርና ነብይ ከሆኑ በኋላ እንኳ ጠላቶቻቸው ከራሳቸው ወገኖች የበለጠ ንብረታቸውን የሚያስቀምጡት ከእርሳቸው ዘንድ ነበር፡፡

በመካ ውስጥ በደረሰ የጎርፍ አደጋ ካዕባ በፈረሰበት ወቅት፤ ዓረቦች ካዕባን ዳግም ገንብተው ነበር፡፡ ሆኖም ግን ሐጀረል አስዋድን (የመካ ጥቁር ድንጋይ) በቦታው የማስቀመጥ ክብር ይገባኛል ጥያቄ ወደ ደም አፋሳሽ ብጥብጥ ውስጥ ለመግባት ጫፍ ደርሰው ነበር፡፡ ሆኖም ግን በነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ዳኝነት በመስማማታቸው ድንቅ ብልሃት ምክንያት ከእልቂትና ከንብረት ውድመት ተርፈዋል፡፡[120]

ነብዩ 25 ዓመት ሲሞላቸው በታማኝነታቸው የተማረከችው ክብርቷ ኸዲጃ የጋብቻ ጥያቄ አቀረበችላቸው፡፡ በአስራ አምስት አመት ትበልጣቸው ነበር፡፡ ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) ጥያቄዋን ተቀብለው፤ ፍፁም ምርጥ ቤተሰብ ለመመስረት ለሚፈልግ ሁሉ ምሳሌ ሊሆን የሚችል ትዳር መሠረቱ፡፡ የወጣትነት ጊዜያቸውን በሙሉ ከኸዲጃ (ረ.አ) ጋር ነበር ያሳለፉት፡፡ ከዲጃ ካለፈች በኋላም ያሉትን አምስት አመታት እንዲሁ ከሳውዳ ጋር አሳለፉ፡፡ ሁለቱም ሴቶች ከዚህ በፊት ያገቡና ዕድሜያቸው የገፋ ነበር፡፡ የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) የጋብቻ ዓላማ ሰብአዊ አሊያም ፖለቲካዊ ግብ ነበረው፡፡ የሁሉም ጋብቻዎቻቸውና ዓላማ ከዚህ አይወጣም፡፡ አንዳንድ ሰዎች እንደሚሉት የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) የትዳር ፍላጎት በ"ሴሰኝነት" የተመራ ቢሆን ኖሮ በወጣትነት ጊዜያቸው በአስራ አምስት አመት ከምትበልጣቸው የልጆች እናት ጋር ተወስነው አያሳልፉም ነበር፡፡[121]

---

120 1Ibn-i Hişâm, I, 209-214; Abdürrezzâk, V, 319.

121 For details on the wisdom of our master the Prophet'smore than one marriage see Osman Nuri TOPBAŞ,*Hazret-i Muhammed Mustafâ,* Istanbul 2008, I, 130-140.

## የነብይነት ጊዜ

ነብዩ አርባ ዓመት ሲሞላቸው አላህ (ሱ.ወ) ለነብይነት ተልዕኮ መረጣቸው፡፡ "አንብብ፣ በዚያ (ሁሉን) በፈጠረው ጌታህ ስም…."[122]

ለተወሰኑ ቀናት ግለሰቦችን ወደ ኢስላም ከጠሩ በኋላ አንድ ቀን በሶፋ ኮረብታ ላይ ወጡና ለቁረይሽ ነገዶች የሚከተለውን ጥያቄ አቀረቡ፡-

"የቁረይሽ ህዝብ ሆይ! ከዚህ ተራራ ጀርባ እናንተን ለማጥቃት ያደፈጠ ጦር አለ ብዬ ብነግራችሁ ታምኑኛላችሁ?" ሰዎቹ "አዎን እናምንሀለን! አንተን እውነት ስትናገር ብቻ ነው የምናውቅህ፣ ሐሰት ከአፍህ የለም" አሉ፡፡ ይሄኔ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ነብይ እንደሆኑና አላህ (ሱ.ወ) አስጠንቃቂ አድርጎ እንደላካቸው አወጁ፡፡ እጅግ ጥልቅ በሆነ ስሜት በእርሳቸው ቃል ያመነና የአላህን ትእዛዝ ተከትሎ መልካም ሕይወት ለመኖር የፈለገ አላህ (ሱ.ወ) በመጪው ዓለም ስኬትን እንደሚያጎናፅፈው ተናገሩ፡፡ የካደ ደግሞ አሳማሚ ቅጣት እንደሚጠብቀው አስጠነቀቁ፡፡ በዚህች ምድር ላይ ሲኖሩ ለሚቀጥለው ዓለም መዘጋጀት እንዳለባቸው አሳሰቡ፡፡ ሆኖም ግን ሰዎችን ለዘመናት ከቆዩበት ዕምነት በቀላሉ ማላቀቅ እንደማይቻል አልተዘነጋቸውም፡፡[123]

ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ሰዎች የእውነትን መንገድ እንዲቀበሉ ያልፈነቀሉት ድንጋይ የለም፡፡ ሰዎችም የዛኑ ያህል መከራና ስቃይ አድርሰውባቸዋል፡፡ ቤት ለቤት ዞረዋል፤ ካዕባን ሊጎበኙ የመጡት ሆነ በገበያ ቦታ የተገኙትን ሰዎችን አናግረዋል፤ ያገኙዋቸውን አጋጣሚዎች በሙሉ ተጠቅመዋል፡፡ ደከመኝ ሰለቸኝ ሳይሉ፣ ቀንደኛ ጠላቶቻቸው ለሆኑት ሳይቀር የኢስላምን እውነት ነግረዋል፡፡ "በርሱም ላይ ምንም ዋጋ አልጠይቃችሁም፡፡ ከአስመሳዮችም አይደለሁም"[124] የሚለውን

---

[122] Al-Alaq (The Blood Clot), 96: 1-2.
[123] See Bukhari, Tefsîr, 26/2; Ahmad bin Hanbal, I, 159, 111.
[124] Sâd, 38: 86.

የአላህን ቃል በማውሳት እርሳቸው መልዕክተኛ ብቻ እንደሆኑ ዘክረዋል፡፡

ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) በዘመናቸው እንደነበሩት አብዛኛዎቹ ሰዎች ማንበብና መፃፍ የማይችሉ መሃይም ነበሩ፡፡[125] ለሰዎች የሚናገሩትን ነገር ከሌሎች መፅሐፍት ሆነ ከሰዎች ተምረውታል ማለት አይቻልም፡፡ ሕይወቱን በሙሉ መሐይም የነበረ ሰው ድንገት ተነስቶ ከዚህ ቀደምም ሆነ በኋላ ተወዳዳሪ ያልተገኘበትን መረጃ እጅግ ድንቅ በሆነ አቀራረብ ለሰዎች መስበክ የሚችለው ወሕይ ከወረደለት ብቻ ነው፡፡ የነብዩ ጠላቶች እንኳን ይህንን መስክዋል፡፡

ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) የሚያውቋቸው ጣኦት አምላኪዎች የነብዩን የመጠቀ ስብእና ስለሚያውቁ እየዋሹ እንዳልነበሩ እርግጠኞች ነበሩ፡፡ ሆኖም ግን በዘረጉት ስርአት የሚያገኙት ቁሳዊ ጥቅም ስለሚቀርባቸው አምርረው ተቃወሙ፡፡ አንድ ጊዜ የነብዩ ቀንደኛ ጠላትና አጎታቸው የነበረው አቡ ጃህል እና ጓደኞቹ ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ያስቆሙዋቸውና "ሙሐመድ ሆይ! በአላህ ይሁንብን በአንተ አንክድም፡፡ አንተ በኛ ዘንድ እጅግ ሐቀኛና እውነተኛ እንደሆንክ እናውቃለን፡፡ የእኛ ችግር በምትናገራቸው አንቀፆች ላይ ነው፡፡ " ብለዋቸው ነበር፡፡[126]

ጣዖት አምላኪዎች ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የያዙትን ተልዕኮ እንዲተው ያልሞከሩት ነገር የለም፡፡ አጎታቸውን በሽምግልና ልከዋል፡፡ ንጉስና ሐብታም ሊያደርጓቸው፤ ከምታምር ሴት ጋር ሊያጋቡዋቸው እንደ መደለያ አቅርበውላቸዋል፡፡ "አንተ የፈለግከውን ልናደርግ ቃል እንገባልሀለን!" እስከማለት ደርሰዋል፡፡ ሆኖም ግን ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) በማያሻማ መልኩ ምላሻቸውን ሰጥተዋል፡፡

"ከናንተ የምፈልገው ነገር የለም፡፡ ሃብትም፣ቁሳቁስም፣ንግስናም ሆነ ሹመት አልፈልግም፡፡ የኔ ብቸኛ ፍላጎት አንድ ብቻ ነው፡፡ ‹ጣኦት

[125] Al-Ankabût (The Spider), 29: 48.

[126] Vâhidî, Esbâbü Nüzûl, p. 219; Tirmizî, Tefsîr, 6/3064.

ማምለካችሁን አቁሙና አላህን ብቻ አምልኩ።" (ኢብን ከሲር፣አልቢዳያ III 99-100)

ጣኦት አምላኪዎቹ የነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ቁርጠኛነት ሲያዩ ወደ ጥቃት ተሸጋገሩ። በየቀኑ በሙስሊሞቹ ላይ የሚያደርሱትን ጭቆናና ስቃይ ማጠናከር ያዙ። አንዳንዶቹ ሙስሊሞች ወደ አቢሲኒያ ተሰደዱ።

ጣኦት አምላኪዎች ከሙስሊሞችና ጠባቂዎቻቸው ጋር ያሉ ማህበራዊ ግንኙነቶች በሙሉ እንዲቋረጡ አደረጉ። ጋብቻም ሆነ ማህበራዊ ግንኙነቶችን ከለከሉ። ይህንንም ከትበው በካእባ ግድግዳ ላይ አንጠለጠሉ። ይህ ማዕቀብ ለሶስት ተከታታይ አመታት ቀጠለ። ሙስሊሞች እጅግ ተሰቃዩ። የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ከዘይድ ኢብን ሐሪስ ጋር ሆነው ከመካ በ160 ኪ.ሜ ርቃ ወደምትገኘው ጧኢፍ ተጓዙ። በዚያም የከተማዋን መሪዎች ሲያነጋግሩ ለ10 ቀናት ቆዩ። ከመሪዎቹ አንዳንዶቹ ከናታቸው ጋር ዝምድና ነበራቸው። ነገር ግን ያገኙት ምላሽ ፈፅሞ ተገቢ ያልሆነ ነበር። ከማንጓጠጥና ከማፌዝ ባሻገር የከተማዋን ወጣቶችና ባሪያዎቻቸውን አሰልፈው በድንጋይ አስደበደቡዋቸው። በዚህ እጅግ የለየለት ጭካኔና ስቃይ ውስጥ ቢሆኑም እንኳን እዝነታቸው ከሰብአዊ በቀል ስሜታቸው በእጅጉ የበለጠ ነበር። ልባቸው ፍፁም ንፁህ ነበር።

"አላህ ሆይ! የአቅሜን ደካማነት፣ የብልሐቴን ጥቂትነት፣ ከሰዎች ዘንድ የተናቅሁ መሆኔን ላንተ ስሞታ አቀርባለሁ። የአዛኞች ሁሉ አዛኝ የሆንከው የደካሞች አምላክ ሆይ! ለማን ትተወኛለህ? ለሚጠሉኝ ባክዮች? ጉዳዩን ከጠላት እጅ አስገባኸውን? አንተ ካልተቆጣህብኝ ግድ የለኝም። ማርታህና ይቅርታህ ይበልጥብኛል። ቁጣህ እንዳይሰፍንብኝ ጨለማን በገሰስክበት ብሩህ ማንነትህ፤ ይህችንም ሆነ መጭውን አለም ባቆምህበት ኃይልና ችሎታህ እጠይቅሃለሁ። ውዴታህን እስካገኝ እደክማለሁ። መላም ሆነ ኃይል ያንተ ቢሆን እንጂ የለም። " (ኢብን ሒሻም II 29-30፣ ሐይታሚ VI 35)

ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ከጧኢፍ መልስ የነበራቸው ጉዞ እንዲህ ይገልፁታል፡፡

"በከፍተኛ ሐዘን ውስጥ ነበርኩ፡፡ ቀርኑል ሳሊም ከሚባል ቦታ ስደርስ እጅግ ደክሞኝ ሰውነቴ ሁሉ ተሳስሮ ነበር፡፡ ቀና ብዬ ወደ ሰማይ ስመለከት ደመና ከፀሐይዋ ጠልሎኝ ተመለከትሁ፡፡ አትኩሬ ስመለከት ጅብሪልን አየሁት፡፡ "አላህ (ሱ.ወ) ህዝቦችህን እንዴት እንዳሰቃዩህና ከለላ ለመስጠት አሻፈረኝ እንዳሉህ አይቷል፡፡ አንተ ያዘዝካቸውን እንዲያደርጉ የተራሮችን መልዐክት ልኳል" አለኝ፡፡ ከዚያም የተራራው መልዓክ ሰላምታ አቀረበልኝ፡፡ ከዚያም "ሙሐመድ ሆይ! … አንተ ያዘዝከኝን እንድፈፅም አላህ (ሱ.ወ) ልኮኛል፡፡ ምን እንዳደርግልህ ትፈልጋለህ? ፍላጎትህ ከሆነ እነዚህን ሁለት ተራሮች አንስቼ አናታቸው ላይ መፈርከስ እችላለሁ" አለኝ፡፡ እኔም "አይሆንም! ልጆቻቸውና የልጅ ልጆቻቸው አላህን ብቻ የሚገዙ እንዲሆኑ እርሱን እለምነዋለሁ" አልኩኝ፡፡" (ቡኻሪና ሙስሊም)

በዚያኑ ሰሞን ከመዲና የመጡ ሰዎች እስልምናን ተቀበሉ፡፡ በመዲናም እስልምናን ማስተማር ጀመሩ፡፡ ስለ ዲኑ የሚያውቅ ሰው እንዲልኩላቸው ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ጠየቁ፡፡ በትንሽ ጊዜ ውስጥ ኢስላም ያልገባበት ቤት አልነበረም፡፡ በመጨረሻም የመዲና ሰዎች ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ወደነርሱ እንዲመጡ ጋበዙዋቸው፡፡ ከለላም እንደሚሰጡዋቸውም ቃል ገቡላቸው፡፡

## የመዲና ጊዜ

ጣዖት አምላኪያን በሙስሊሞች ላይ እያደረሱ ያሉት ስቃይና መከራ ከፍተኛ ደረጃ ላይ ሲደርስ፣ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ለተከታዮቻቸው በድብቅ ወደ መዲና እንዲሰደዱ ነገሩ፡፡ ይህን የተረዱት ጣዖት አምላኪያን የነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ብቸኝነት ተገንዝበው ሊገድሉዋቸው ማሴር ጀመሩ፡፡ ከእያንዳንዱ ነገድ አንድ አንድ ወጣት መለመሉና ሁሉም እኩል በመሳሪያ እንዲመቱዋቸው ተስማሙ፡፡ ዕቅዱ ከግድያው በኂላ የሚነሳን

የበቀል ጦርነትን ለመከላከል የታሰበ ነበር፡፡ በዚህ ወቅት አላህ (ሱ.ወ) ነብዩን እንዲሰደዱ አዘዛቸው፡፡ የአላህ መልዕክተኛ ከእርሳቸው ዘንድ ንብረታቸውን ያስቀመጡት ለየባለቤቶቻቸው እንዲመልስላቸው ዓሊን (ረ.ዐ) ወከሉ፡፡[127]

የዛን ዕለት ምሽት ነፍስ ገዳዮች የነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ቤት ከበቡ፡፡ ነገር ግን ሁሉም ተኙ፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ከያሲን ምዕራፍ የመጀመሪያዎቹን አንቀፆች እያነበቡ በመካከላቸው አለፉ፡፡ ማንም ያያቸው አልነበረም፡፡ ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ከ13 የጥሪ ዓመታት በኋላ ወደ መዲና ተሰደዱ፡፡

መዲና እንደደረሱ የመዲናን ሰዎች ከመካ ሰዎች ጋር ወንድማማች አደረጉ፡፡ መዲናዎችም (አንሷሮች) "ንብረቴ ይኸውልህ፣ ግማሹ ያንተ ነው" እያሉ ለመካዎች (ሙሐጀሮች) በሮቻቸውን ወለል አድርገው ከፈቱ፡፡ መብቃቃት የነገሰባት የሙሐጂሮች ልብ ግን ምላሹ ይህ ነበር፡- "ንብረትህ የተባረከ ይሁን ወንድሜ ሆይ! የገበያውን መንገድ ካሳየኸኝ በቂ ነው!" [128]

በመዲና ነዋሪ የሆኑትን ሙሐጀሮችን፣ አንሳሮችንና አይሁዶችን ሊያስተዳድር የሚችል ሕገ መንግሥት ተቀረፀ፡፡ ይህ በዓለም ታሪክ ውስጥ የመጀመሪያ በፅሁፍ የተዘጋጀ ሕገ መንግስት ነው፡፡ [129]

በኢስላም ቅድመ ታሪክ የተካሄዱት ጦርነቶች በሙሉ ምክንያታቸው ጣዖት አምላኪዎች በሙስሊሞች ላይ የፈፀሙት ተደጋጋሚ ትንኮሳ ነበር፡፡ ጣዖት አምላዎኪዎች ከሙስሊሞች ጋር የገቡዋቸውን ውሎችና ስምምነቶች በሙሉ አፍርሰው ነበር፡፡ በዚህ ምክንያት ነቢዩም ሆኑ ሙስሊሞች ወዳልፈለጉት፣ ነገር ግን ወደማይቀረው ጦርነት ገቡ፡፡ ነገር ግን ነብዩና ሙስሊሞች ያደረጉዋቸው ጦርነቶች በሙሉ እዝነት

---

127 Ibn-i Hishâm, II, 95, 98.

128 Bukhari, Büyû, 1.

129 M. Hamîdullah, *The First Written Constitution in the World,* Lahore 1975.

ተለይቶት አያውቅም ነበር፡፡ ምንም እንኳን ዐረቢያ በሙሉ በነብዩና በሙስሊሞች ቁጥጥር ስር ብትሆንም የበቀል ስሜት እንዳይኖርና ደም መፍሰስ እንዳይከሰት አድርገዋል፡፡ በየትኛውም ወቅት የሚፈጠሩ አለመስማማቶችና ችግሮች በንግግርና በስምምነት እንዲፈቱ ጥረት ያደርጉ ነበር፡፡

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) 29 በሚሆኑ ወታደራዊ ዘመቻዎች ላይ ተሳትፈዋል፡፡ አስራ ስድስቱን ምንም አይነት አካላዊ ግጭት ውስጥ ሳይገቡ በስምምነት ጨርሰዋቸዋል፡፡ በ13 ላይ ግን ውጊያ ያደረጉ ሲሆን በነዚህ ጦርነቶች ውስጥ 140 ሙስሊሞች ሰማዕት ሲሆኑ ከጠላት ወገን 335 ሰዎች ሞተዋል፡፡[130]

የኢስላም የጦርነት ዓላማ ሰዎችን መግደል፣ምርኮን መሰብሰብ፣ የግል ወይም ቁሳዊ ጥቅሞችን አሊያም በቀል ለመሻት አይደለም፡፡ የኢስላም ጦርነት ዓላማ ጭቆናን ማስወገድ፣ የእምነት ነፃነትን ማስፈን፣ ሰዎች ቀጥተኛውን መንገድ እንዲመለከቱ የአስተሳሰብ ነፃነታቸውን እንዲጠቀሙ ምቹ ሁኔታዎችን መፍጠርና ኢ ፍትሀዊነትን ማስወገድ ብቻ ነው፡፡

## ተወዳዳሪ የሌለው ስነ ምግባራቸው

የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) እዝነት ለሰዎች ብቻ የተገደበ ሳይሆን ለተክሎችና እንስሶችም ጭምር የተረፈ ነው፡፡ ጣኦት አምላኪዎች ስምምነታቸውን በመጣሳቸው ምክንያት ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) አስር ሺ ወታደሮች ይዘው ወደ መካ ይዘምታሉ፡፡ በጉዞ ላይ ሳሉ ባታሉክ አካባቢ አርጅ በሚባል ቦታ ላይ ሲደርሱ አንዲት እመጫት ውሻ ተዘርግታ ልጆቿን ስታጠባ

130 See Prof. Dr. M. Hamidullah, *Hz. Peygamber'in Savaşları(The Battles of HE the Prophet),* Istanbul 1991; Dr.Elşad Mahmudov, *Sebep ve Sonuçları Itibâriyle Hazret-I Peygamber'in Savaşları (The Battles of HE Prophet in terms*

ተመለከቱ፡፡ ወዲያውኑ ጃአይል ቢን ሹራካን ጠሩትና ውሻዋ በሰራዊቱ እንዳትረበሽ እንዲጠብቋት አዘዙ፡፡[131]

አንድ ጊዜም ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በአንድ አንሷር አትክልት ቦታ ሲያልፉ አንድ ነገር ያቆማቸዋል፡፡ አንድ ግመል ነብዩን ሲመለከት ማልቀስና ማጓራት ይጀምራል፡፡ ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) ወደ ግመሉ ሄዱና ጆሮው ስር አሻሹት፡፡ ግመሉም ተረጋጋ፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ግን "ይህ ግመል የማን ነው?" ሲሉ ጠየቁ፡፡ አንድ ወጣትም ቀርቦ "የኔ ነው የአላህ መልዕክተኛ" አላቸው፡፡ ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) "አላህ በሰጠህ እንሰሳ ጉዳይ እርሱን አትፈራምን? በበቂ ሁኔታ እንደማትመግበውና ሥራም እንደምታበዛበት ነግሮኛል!" ሲሉ አስጠነቀቁት፡፡ (አቡ ዳውድ፣ ጂሃድ 44/2549)

ሌላ ጊዜ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) አንድ ሰው ሊያርደው ባዛጋጀው በግ ፊት ቢላዋ ሲስል ይመለከታሉ፡፡ ሰውየውን "ሁለቴ ልትገድለው ትፈልጋለህ? ለምን በጉ ሳያይህ ቢላዋን አትስልም" ሲሉ አስጠነቀቁት፡፡

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ምንም እንኳን የመቅጣትና ብድርን የመመለስ ኃይል ቢኖራቸውም፣ ከፍተኛ ስቃይና መከራ ያደረሱባቸውን ሰዎች ይቅር ብለዋል፡፡ ሌላው ይቅርና በቃላት እንኳን ሊገስፁዋቸው ሆነ ሊያሳቅቋቸው አልፈለጉም፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) አማኝንም ሆነ ኢአማኒያንን መጉዳት አይፈልጉም፡፡ ማንንም ሳይለዩ ለሁሉም ምርጥ ባህሪያቸውን አሳይተዋል፡፡ መካን ያለምንም ደም መፋሰስ ሲይዙ ለዓመታት መሪር ጠላቶቻቸው የነበሩት የመካ ነዋሪዎች ከነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ፊት ቀርበው የሚሏቸውን ይጠባበቁ ነበር፡፡ ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) "የቁረይሽ ሰዎች ሆይ! ምን የማደርጋችሁ ይመስላችኋል? ሲሉ ጠየቋቸው፡፡ እነርሱም "አንተ በኛ ዘንድ የተከበርክ ሰው ነህ፤ ካንተም የምንጠብቀው የተከበረ ነገር ነው፡፡" አሉ፡፡ ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) "ዮሴፍ (ዐ.ሰ) ለወንድሞቹ ‹ዛሬ በናንተ ላይ ወቀሳ የለባችሁም፤ አላህ ለናንተ ይምራል፤ እርሱም ከአዛኞቹ ሁሉ

[131] Vâkıdî, II, 804.

ይበልጥ አዛኝ ነው›[132] እንዳላቸው እኔም ይህንኑ እላቸዋለሁ። ሂዱ ነፃ ናችሁ!" አሏቸው።

የዛን ቀን በዑሑድ ጦርነት ጊዜ እጅግ የሚወዷቸውን አጎታቸውን የሐምዛን ልብ ያኘከችውን ሒንዱንም ይቅር ብለዋታል። ሌላው ይቅርና ልጃቸውን ዘይነብን (ረ.ዐ) የገደላት ሂብር ኢብን አስዋድ ምህረትን አግኝቷል።[133]

የአላህ መልዕክተኛ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) እጅግ ትሁት ነበሩ። መካ በተከፈተችበት ወቅት፤ በሰዎች ዘንድ እንደ ሃይለኛ ሰው በታዩበት ወቅት አንድ ሰው ወደ እርሳቸው እየተንቀጠቀጠ ቀረበ። ነብዩም "ተረጋጋ! ንጉስም ገዢም አይደለሁም። እኔ ቋንጣ ስጋ የምትበላ የቁረይሽ ሴት ልጅ ነኝ!" ብለው አረጋጉት። (ኢብን ማጃህ አይታም 30፣ ሐኪም III 50/4366)

ተከታዮቻቸውን "የአላህ ባሪያና መልዕክተኛ" ብላችሁ ጥሩኝ ይሉ ነበር።[134] ሰዎች ነብይነታቸውን ምስክርነት ለመስጠት ሲመጡ "አብዱሁ" (ባሪያው) የሚለውን መለያቸውን እንዲሉ ያደርጉ ነበር። ይህን የሚያደርጉት ሕዝቦች ዳግም ለሰው መለኮትን ከመስጠት እንዲቆጠቡ (እንዲታቀቡ) ለማድረግ ነበር። በሰዎች ዘወትር “ከሚገባኝ በላይ ደረጃ አትስጡኝ። እኔ በአላህ ፊት ባሪያውና መልዕክተኛው ነኝ" ይሉ ነበር። (ሐይታሚ II 21)

አቡ ዑማማ (ረ.ዐ) እንዲህ ይላል፡- "የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ንግግራቸው በሙሉ ስለ ቁርአን ነበር። (ስለ ቁርአን ያወራሉ፤ ያብራራሉ።) የአላህንም ስም በተደጋጋሚ ያወሳሉ። ተራ ንግግር ውስጥ አይገቡም። ስብከታቸውን ትንሽ፣ አምልኮዋቸውንረዘም ያደርጋሉ። ባለቤቷ ከሞተባት ሴት ጎን ለመሄድ ቅሬታ አይገባቸውም። ከድሆች ጋር ከመሆንና ችግሮቻቸውን

---

132 Yûsuf (Joseph), 12: 92.
133 Muslim, Akdıye, 9; Vâkıdî, II, 857.
134 Bukhari, Anbiyâ, 48.

ከመፍታት ወደ ኋላ አይሉም፡፡ በፍፁም እብሪተኛም አልነበሩም፡፡" (ሐይታሚ II 20፡ ነሳዒ፣ጁምዓ 31)

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) በርህራሄ፣ ጨዋነትና ሽክታ ምሳሌ ናቸው፡፡ ልብሳቸው ንጹህና ሥርዓታማ እንደሆነ ያረጋግጡ ነበር፡፡ ዝርክርክነትን አይታገሱም፤ የፀጉርና ፂምን ዝብርቅርቅነት አያበረታቱም፡፡ ከአፋቸው የብልግና ቃል ተሰምቶ አይታወቅም፡፡

"የፍርድ ቀን ከመልካም ባህሪ የበለጠ የስራን ሚዛን ከባድ የሚያደርግ የለም፡፡ አላህ (ሱ.ወ) መጥፎ እንቅስቃሴን የሚያደርግንም ሆነ የብልግና ቃላትን የሚናገርን ሰው አይወድም" ብለዋል፡፡ (ቲርሚዚ፣ ቢር 62/2002)

አንድ ሰው ያልተገባ ነገር ተናግሯል ወይም አድርጓል የሚባልን ነገር ሲሰሙ "እከሌ እከሌ" ብለው የሰሙትን ስም ጠርተው በአደባባይ አያዋርዱትም (አይገስፁትም) ነበር፡፡ እንዲህ ነበር የሚሉት "ለምንድን ነው አንዳንድ ሰዎች እንዲህ የሚሉት ወይም የሚያደርጉት" (አቡ ዳውድ፣ አዳብ 5/4788)

በአላህና በመልዕክተኛው ትዕዛዝና ሕግጋት አማካኝነት የሴቶች ደረጃ ወደ ፍፁም ተምሳሌትነት ተሸጋግሯል፡፡ በዚህም ምክንያት ሴቶች በጨዋነትና ፃድቅ ተምሳሌት ለመሆን በቅተዋል (ችለዋል)፡፡ እናትነት ክብር አግኝቷል፡፡

"ጀነት በእናታችሁ እግር ስር ነው"[135]በሚለው የነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ንግግር እናቶች እንደ እምነት መሠረት ሆነዋል፡፡ አይሻ (ረ.ዐ) እንደመሰከረችው ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ባለቤታቸውን በምንም አይነት መልኩ ረብሸው፤ በእጃቸውም አንድ ሰው ጎድተው አያውቁም፡፡[136]

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ቸር ነበሩ፡፡ ከመካ ጣዖት አምላኪዎች መካከል ሰፍዋን ኢብን ዑመያህ ከተከበሩ ባለሚሎች አንዱ ነበር፡፡ ምንም እንኳን በወቅቱ

---

135 Nesai, Jehad, 6; Ahmad bin Hanbal, III, 429.
136 Ibn-i Majah, Nikâh, 51.

ሙስሊም ባይሆንም በሁነይን እና ጧኢፍ ጦርነቶች ላይ ከሙስሊሞች ጋር ተዋግቷል፡፡ ነብዩ በጂራናህ ሞርኮ እየተመለከቱ ሳለ ሰፍዋን የበግ መንጎችን በአድናቆት ሲመለከት አዩትና "ፈልግሃቸው እንዴ? ሲሉ ጠየቁት፡፡ ሰፍዋንም በአዎንታ መለሰ፡፡ ነብዩም "ውሰዳቸሁ፣ ሁሉም ያንተ ነው!" አሉት፡፡ ሰፍዋን ራሱን መቆጣጠር አልቻለም፡፡ በአድናቆት እንደተዋጠ፡- "ከነብይ ውጭ ማንም እንዲህ ቸር መሆን አይችልም!" አለና እስልምናን ተቀበለ፡፡[137]

ታዲያ ወደ ነገዱ ሲመለስ እንዲህ ብሎ ነበር፡- "ሰዎቼ ሆይ! (በፍጥነት) ሙስሊም ሁኑ፡፡ ሙሐመድ ታላቅ ቸርነት እያሳየና ስጦታ እየሰጠ ነው፡፡" (ሙስሊም ፈዳይል 57-58፣ አሕመድ ኢብን ሐንበል III 107-108)

የአላህ መልዕክተኛ ከዚህ ዓለም በሞት የተለዩት በጁን 8፣ 632፤ በኢስላማዊ አቆጣጠር በ11ኛው ዓመት ሂጅራ በወርሃ ረቢዓል አወል በ12ኛው ቀን ነበር፡፡

ወደ መዲና በስደት ከመጡ በአስር አመታት ውስጥ ከኦማን እስከ ቀይ ባህር፣ ከየመን እስከ ደቡብ ሶሪያ ያካለለ የፅድቅ ስርዓት ገነቡ፡፡ ዓረቦች በታሪክ ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ አንድ ሆኑ፡፡ ፈረንሳዊው አብሰልሳይ ስለ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ)እንዲህ ነበር ያለው፡፡

"በውስን ግብዓት ታላቅ ግብን ሰንቆ ታላቅ ውጤትን ማምጣት የታላቅ ሰውነት መለኪያዎች ናቸው፡፡ በዚህ በኩል በዘመናት ታሪክ ውስጥ ከታላቁ ሙሐመድ ጋር የሚወዳደር ማን አለ?" [138]

## ወሰን የሌለው ፍቅራቸው

እኛ ሙስሊሞች ከነፍሳችን የበለጠ ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) እንወዳለን፡፡ ሰሃባዎች ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) ሲያናግሩ "እናትና አባቴ ፊዳ ይሁንልዎ"[139] ይሉ ነበር፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) እሾህ ከሚወጋቸው ቢሞቱ ይመርጣሉ፡፡

---

137 Vâkıdî, II, 854-855.

138 A. de Lamartine, *Histoire de la Turquie*.

ጣዖት አምላኪያኑ ዘይድ ኢብን ዓሲናንና ሁበይብን (ረ.ዐ) ለሞት በሚያደርስ አኳኋን እያሰቃዩዋቸው ባሉበት ወቅት ለእያንዳዳቸው የሚከተለውን ጥያቄ አቀረቡላቸው፡- "ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ባንተ ቦታ ቢሆኑ ትመርጣለህ?" የሁለቱም መልስ ይህ ነበር "ለርሳቸው ደህንነት ሲባል ቤተሰቦቼና ልጆቼ መስዋእት እንዲሆኑላቸው ብቻ ሳይሆን የምመኘው፤ አሁን ባሉበት ቦታ እንኳን እሾህ ቢወጋቸው ልቤ አያርፍም።" በዚህ ተወዳዳሪ በሌለው ፍቅር የተደነቀውና የደነገጠው አቡ ሱፊያን በበኩሉ ይህን ብሎ ነበር "የነብዩ ጓዶች ነብዩን ሚያፈቅሯቸውን ያክል ጓደኛውን የሚያፈቅር አላየሁም።"

ይህን ወደር የለሽ ፍቅር ስማቸው በተነሳና ንግግራቸውን ባወሱ ቁጥር ማየት ይቻላል። የነብዩ ጓዶች ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ከተናገሩት ንግግር ሲያወሱ የርሳቸው ያልሆነን ቃል ላለመጨመር በፍርሀት ጉልበታቸው ይብረከረክ፣ ፊታቸው ይገረጣ ነበር። አምር ኢብን መይመን ይህንን አስተላልፏል፡-[140]

"ኢብን መስዑድ ሐሙስ ማታ የሚያደርጉት ንግግር አምልጦኝ አያውቅም። በየትኛውም ጉዳይ ላይ ሲያወጉ የአላህ መልዕክተኛ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲህ ብለዋል፡- በማለት ሲናገሩ ሰምቻቸው አላውቅም ነበር። ነገር ግን በአንድ የሐሙስ ምሽት ‹አለቃችን የአላህ መልዕክተኛ ብለዋል› አሉ። ወዲያው ንግግራቸውን አቆመውና ጭንቅላታቸውን ዝቅ አደረጉ። ከትንሽ ቆይታ በኋላ ተመለከትኩላቸው። የቀሚሳቸውን ቁልፎች ፈቱ፤ እያለቀሱ ነበር፤ ጉንጫቸውም አብጠው ነበር። ከዚያም ንግግራቸውን እንዲህ ሲሉ ጨረሱ "የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) …"[141]

---

139 Translator's note: An Arabic saying expressing love for someone.

140 Vâkıdî, I, 360-362; Ibn-i Sa'd, II, 56.

141 Ibn-i Majah, Muqaddime, 3. For rich examples of the boundlesslove for our master the Prophet throughout history see Osman Nuri Topbaş, *Faziletler Medeniyeti (Civilization of Virtues),* I, 223-265; http://www.islamiyayinlar. net/content/view/148/8/

## ተአምራቶቻቸው

በነቢያችን (ሰ.ዐ.ወ) እጆች ለቁጥር የሚያታክቱ ተዓምራት ተሰርተዋል፡፡ የተወሰኑትን እንደሚከተለው እናቀርባቸዋለን፡፡

ጃቢር (ረ.ዐ) እንዲህ ይላል፡- "በሁዴቢያ ጊዜ ሰዎች ተጠሙና ወደ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) መጡ፡፡ ከአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ፊት ውሃ የያዘ አነስ ያለ ስልቻ ተቀምጧል፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ውዱዕ እያደረጉበት ነበር፡፡ ሰዎች ሲጠጉዋቸው "ምን ችግር ገጠማችሁ?" ሲሉ ጠየቋቸው፡፡ ሰዎቹም "እርሶ ውዱእ እያደረጉበት ካለው በስተቀር ለመጠጥም ለውዱዕም የሚሆን ውሃ የለም" አሉ፡፡ የአላህ መልዕክተኛም (ሰ.ዐ.ወ) እጃቸውን ከስልቻቸው ውስጥ ከተቱና አወጡት፡፡ ከጣቶቻቸው ልክ እንደ ምንጭ ውሃ መፍለቅ ጀመረ፡፡ ሁላችንም እስክንረካ ጠጣን" ውዱዕም አደረግን፡፡

ጃቢር "ምን ያህል ሰዎች ነበራችሁ?" ተብሎ ሲጠየቅ "በመቶ ሺዎች የምንቆጠር ብንሆንም እንኳ፣ ውኃው ይበቃን ነበር፡፡ እኛ ግን አንድ ሺህ አምስት መቶ ነበርን" ብሎ መልሷል፡፡[142]

ቁረይሾች ነብዩን (ሰ.ዐ.ወ) "ተዓምር አሳየን" ባሉ ጊዜ የአላህ መልዕክተኛ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ወደ አላህ ፀለዩና ጨረቃን ለሁለት ከፈሏት፡፡ ለሁለት የተከፈለችው ጨረቃ አንደኛው ክፋይ በአቡ ኩበይስ ተራራ በላይ ሲታይ ሌላኛው ክፋይ ደግሞ ከኩዩኬን ተራራ በላይ ታይቷል፡፡ ጣዖት አምላኪዎች ስለ ሁኔታው ከሩቅ አገር መጥተው መካ አካባቢ ያረፉትን ሲራራ ነጋዴዎች ሲጠይቁ፣ እነርሱም ክስተቱን እንዳዩ መሰከሩ፡፡ ጨረቃም ለሁለት ተገምሳ እንደተመለከቱ አስታወቁ፡፡[143]

---

142 Bukhari, Menâkıb, 25. In this source, many more miracles of the Messenger of Allah (blessings and peace be upon him) are cited.

143 Al-Qamar (The Moon), 54: 1-3; Bukhari, Menâkıb 27, Menâkıbu'l-Ensâr 38, Tefsîr 54/1; Muslim, Munâfıkîn, 43, 47, 48; Tirmizî, Tefsîr, 54/3286; Ahmad bin Hanbal, I,377, 413.

ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ደገፍ ብለው ኃይማኖታዊ ዲስኩር የሚያደርጉበት አንድ ጉቶ ነበር፡፡ ሚንበር ከተሰራ በኋላ ሁሉም ሰው በሚሰማው አኳኋን ጉቶው "ከነብዩ ጋር ተለያየሁ" ብሎ ማልቀስ ጀመረ፡፡[144]

አቡ ሁረይራ (ረ.ዐ) በዘገቡት ሀዲስ ይህ ተከስቷል፡፡ "በአንድ ዘመቻ ላይ ከነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ጋር ነበርን፡፡ የወታደሮች ስንቅ አለቀ፡፡ ወታደሮቹ የጋማ ከብቶቻቸውን ለማረድ ተነሱ፡፡ዑመር (ረ.ዐ) ‹የአላህ መልዕክተኛ ሆይ! የተረፈውን እህል ሰብስቤ እርሶ እንዲበዛ ዱአ ቢያደርጉበት አይሻልምን?› ሲል ሃሳብ አቀረቡ፡፡ ነብዩም (ሰ.ዐ.ወ) ይህን ሃሳብ ወደዱት፡፡ ስንዴ ያለው ስንዴውን፣ ተምር ያለው ተምሩን፣ የተምር ፍሬ ያለው እርሱንም አመጣ"
አቡ ሁረይራን ሲያደምጡ ከነበሩት ሰዎች መካከል "የተምር ፍሬ ምን ሊያድርግላቸው ያዙ? ሲሉ ጠየቁ፡፡አቡሁረይራም "ሰዎች የሚበሉት ሲያጡ፣ ፍሬውን ከአፋቸው ውስጥ አድርገው ከመጠጡ በኋላ ውሃ ይጠጣሉ፡፡" ብለው ከመለሰ በኋላ ታሪኩን እንዲህ ቀጠሉ፡- "የአላህ መልዕክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) ዱዓ አደረጉ፡፡ የምግብ አቅርቦቱ እጅግ ተትረፈረፈ፤ ሁሉም ሰው ኮታውን ሞላ፡፡ ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) ከዚህ በኋላ የሚከተለውን አሉ፡፡ ‹ከአላህ ሌላ አምላክ እንደሌለ፤ እኔም የእርሱ መልዕክተኛ እንደሆንኩ እመሰክራለሁ፡፡ በነዚህ ሁለት ነገሮች ላይ ሳይጠራጠር ከአላህ ጋር የተገናኘ ጀነት ይገባል›"[145]

---

144 Bukhari, Menâkıb, 25; Tirmizî, Jum'a 10, Menâkıb 6; Nesâî, Jum'a, 17; Ibn-i Majah, Ikâme, 199; Dârimî, Muqaddime 6, Salât 202; Ahmad bin Hanbal, I, 249, 267, 315, 363.

145 ሙስሊም ኢማን 44 በነብዩ ሕይወት፣ሞራልና ተዓምራት ላይ የበለጠ ለማወቅ የሚከተለውን ምንጮችተመልከቱ፡-
http://www.islamiyayinlar.net/content/view/36/8/http://www.islamicpublishings.net/images/book/ingilizce/Rahmetesintileri_ing.pdfhttp://hazretimuhammedmedinedevri.darulerkam.altinoluk.com/Ibn Ishaq (150/767), *The life of Muhammed,* Karaçi: Oxford
University, 1967; Mevlana Şibli en-Numani, *Siretü'n-Nebi=The life of the Prophet,* Lahor: Kazı Publications,1979; Afzalurrahman, *Encyclopaedia of seerah: Muhammed,*London: The Muslim Schools Trust, 1982; AbdulahadDawud, *Mohammad in the Bible*, Devha [Doha]:
A Publications of Presidency, 1980; Martin Lings, *Muhammad:his life based on the earliest sources,* London: TheIslamic Texts Society, 1983; A. H. Vidyarthi, *Mohammad in world scriptures,* New Delhi: Deep-Deep Publications,1988.

# ማጠቃለያ

ይህቺ መፅሐፍ እንደ ውቅያኖስ ላይ ጠብታ ኢስላምን በጨረፍታ ለማሳየት ሞክራለች ። ኢስላምን ቀረብ ብሎ ለተመለከተው ተነግሮ የማያልቅ ውበት ያለው ነው። ነገር ግን፣ በሚያሳዝን አኳኋን ዛሬ ሆን ተብሎም ይሁን ባለማወቅ ኢስላም በተሳሳተ መንገድ ለሰዎች እየቀረበ ነው። በዚህም ምክንያት ውበቱ እንዲከለል ሆኗል። ሆኖም የትኛውም ብልህ ሰው ኢስላምን ከዋናው ምንጭ በማንበብ ምሉዕ ይዘቱን መረዳት ይችላል።